ወይትኀጐሉ ፡ በመዓት ፤
በቁጣ ፡ ይጠፋሉ ፤
ወበኵነኔ ፡ ኃያል ፡ አንተ ፡ ለዓለም ፤
ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ በጽኑ ፡ ፍርድ ፤ አንድም ፡ በኃያል በእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ አንድ ሁነው ፡ ይጠፋሉ ፤
፴፰ ፤ ወይትነሣእ ፡ ጻድቅ ፡ እምንዋም ፤
ጻድቅ ፡ ማናቸውም ፤ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ከንዋመ ፡ ኃጢአት ፤ ከንዋመ ፡ ሐኬት ፡ ይነሣል ፤ አንድም ፡ ጌታ ፡ ከንዋመ ፡ ትዕግሥት ፡ ይነሣል ፤
ወይትነሣእ ፡ ጥበብ ፡
ጥበብ ፡ ይገለጻል ፡
ወይትወሀብ ፡ ሎሙ ፤
ለሎጥ ፡ ለልጆቹ ፡ ይሰጣል ፤
ወእምኔሁ ፡ ይትገዘሙ ፡ አሥራወ ፡ ዓመፃ ፤
ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰብአ ፡ ሰዶም ፤ ሰብአ ፡ ገሞራ ፤ ከሎጥ ፡ ተለይተው ፡ ይጠፋሉ ፤
፴፱ ፤ ወኃጥአን ፡ ይትኀጐሉ ፡ በሰይፍ ፤
ሰብአ ፡ ከነዓን ፡ በሰይፈ ፡ ኢያሱ ፡ ይጠፋሉ ፤
ወእምነ ፡ ጽሩፋን ፡ ይትገዘሙ ፡ በኵሉ ፡ መካን ፤
እግዚአብሔርንም ፡ የሚሳደቡ ፡ ወገኖች ፡ ከየቦታው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋሉ ፤
፵ ፤ ወእለ ፡ ይሔልይዋ ፡ ለግፍዕ ፡ ወእለ ፡ ይገብርዋ ፡ ለጽርፈት ፡ ይትኀጐሉ ፡ በመጥባሕት ፤
ግፍን ፡ የሚያስቧት ፡ ስድብንም የሚሳደቡ ፡ ሰብአ ፡ ከነዓን ፡ በመጥባሕተ ፡ ኢያሱ ፡ ይጠፋሉ።

## ምዕራፍ ፴፭
## ጉባኤ

፩ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ትከውን ፡ ካልዕት ፡ ሰንበት ፡ ሳምኒት ፡ እንተ ፡ ጽድቅ ፤
እውነተኛ ፡ ምሥጢር ፡ የሚገለጽባት ፡ ሁለተኛ ፡ የምትሆን ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ስምንተኛ ፡ ሱባዔ ፡ ትሆናለች ፤ ካልዕት ፡ ለ፩ኛው ፤ ሳምኒት ፡ ለመጀመሪያው ፡ ነው ፤ ውስጥ ፡ ለውስጥም ፡ ሱባዔ ፡ ሲቈጥር ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፤ ለዚያ ፡ ሳምንት ፤ ካልዕት ፡ አለ ፤ ሱባዔው ፡ የውሉድ ፡ ነውና ፤ ኢዮስያስ ፤ ኢዮአቄም ፡ ኢኮንያን ፤ ሰላትያል ፤ ዘሩባቤል ፤ አብዩድ ፤ ኤልያቄም ፤ ናቸው ፤
ወይትወሀብ ፡ ላቲ ፡ ሰይፍ ፤
ለትሩፍ ፡ ሥልጣን ፡ ይሰጣታል ፤
ከመ ፡ ይትገበር ፡ ኵነኔ ፡ ጽድቅ ፡ እምእለ ፡ ይገፍዑ ፡ ወይትሜጠዉ ፡ ኃጥአን ፡ በእደዊሆሙ ፡ ለጻድቃን ፤
በሚበድሉ ፡ በፋርስ ፡ በባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡

ይደረግ ፡ ዘንድ ፤ ኃጥአን ፡ በጻድቃን ፡ እጅ ፡ ይወድቃሉ ፤ አንድም ፡ በትሩፋን ፡ እጅ ፡ የባቢሉን ፡ ሰዎች ፡ ይወድቃሉ ፤

፪ ፤ በተፍጻሜታ ፡ ያጠርዩ ፡ አብያተ ፡ እምጽድቀ ፡ ዘአሆሙ ፤

በሱባዔው ፡ መጨረሻ ፡ ትሩፋን ፡ ቤት ፡ ንብረት ፡ ያበጃሉ፤ አንድም ፡ ብዕለ ፡ አሕዛብን ፡ ይሰበስባሉ ፤ አንድም ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ይሠራሉ ፤

ወይትሐነጽ ፡ ቤት ፡ ለንጉሥ ፡ ዓቢይ ፡ ለስብሐት ፡ እስከ ፡ ለዓለም፤ ዓቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሊመሰገንበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይሠራል ፤

፫ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሰንበት ፡ ታስዕት ፡ ባቲ ፡ ከነኔ ፡ ጽድቅ ፡ ትትከሠት ፡ ለኵሉ ፡ ዓለም ፤

ስምንተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ በዘጠነኛው ፡ ሱባዔ ፡ እውነተኛ ፡ ምሥጢር ፡ ይገለጽባታል ፤ አዛር ፤ ሳዶቅ ፤ አኪን ፤ ኤልዩድ ፤ አልዓዛር ፤ ማትያን ፤ ያዕቆብ ፡ ናቸው ፤

፬ ፤ ወኵሉ ፡ ተግባረ ፡ ረሲዐን ፡ ይወዕእ ፡ እምዲበ ፡ ምድር ፤

ጣዖት ፡ አንጥያኮስ ፡ ይጠፋል ፤

ወይጸሐፍ ፡ ለኃጕል ፡ ዓለም ፤

ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለጥፋት ፡ ይቈጠራል ፤

ወኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ይኔጽሩ ፡ ለፍኖተ ፡ ርትዕ ፤

ሰው ፡ ሁሉ ፡ የቀናች ፡ ሕገ ፡ ኦሪትን ፡ ይመለከታል ፤

፭ ፤ ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ በሰንበት ፡ አሥርት ፤

ከዘጠነኛው ፡ ሱባዔ ፡ በኋላ ፡ ባሥረኛው ፡ ሱባዔ ፤

፯ቱ ፡ እድ ፡ ባቲ ፡ ኰነኔ ፡ እንተ ፡ ለዓለም ፤

ለዘለዓለሙ ፡ ጸንታ ፡ የምትኖር ሰባት ፡ እጅ ፡ ፍጹም ፡ ፍርድ ፡ ይሆንባታል ፤

፮ ፤ ወትትገበር ፡ እምትጉሃን ፤

በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ፍርድ ፡ ይደመራል፤

ወሰማይ ፡ ዘለዓለም ፡ ዓቢይ ፡ ዘይበቍል ፡ እማእከሉሙ ፡ ለመላእክት ፤

በመላእክት ፡ መካከል ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ መንግሥት ፡ ሰማይ ፡ ይሰጣል ፡ ይባላል ፤ ነስሑ ፡ እስመ ፡ ቀርበት ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ተብሎ ፡ ይነገራል ፤ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ መከራ ፡ ይጸናል ፤ አለ ፤ ጌታ ፡ በተወለደ ፡ ጊዜ ፡ ፍዳ ፡ ጸንቶባቸዋልና ፤ ጌታንና ፡ ዮሴፍን ፡ በፍጹም ፡ ቈጥሮ ፤ አንድም ፡ ጕንዱ ፡ አልዓዛር ፡ ነው ፤ አልዓዛር ፡ ማትያንና ፡ ቅስራን ፡ ይወልዳል ፤ ማትያን ፡ ያዕቆብን ፤

ያዕቆብ ፡ ዮሴፍን ፡ ሦስት ፤ ቅስራ ፡ ኢያቄምን ፤ ኢያቄም ፡ እመቤታችንን፡ሦስት ፤ ጌታ ፡ ፯ኛ፡ ነው ፤ እንዲህም ፡ አድርጎ ፡ ሱባዔ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ሲቆጥር ፡ አበውም ፡ አብረው ፡ ተቈጥረዋል፤ ሴትንስ ፡ ከወንድ ፡ አግብተው ፡ አይቈጥሩም ፡ ብሎ ፡ ባለፈው ፡ ያጸኗል ፤

፯ ፤ ወሰማይ ፡ ቀዳማዊ ፡ ይወፅእ ፡ ወየኀልፍ ፤

የቀድሞው ፡ ሰማይ ፡ ጠፈር ፡ ያልፋል ፡ ይባላል ፤

ወሰማይ ፡ ሐዲስ ፡ ይትረአይ ፤

መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰጣል ፡ ይባላል ፡

ወኵሉ ፡ ኃይላተ ፡ ሰማያት ፡ ያበርሁ ለዓለም ፡ ፯ተ ፡ ምክዕቢተ ፤

የሰማይ ፡ ሠራዊት ፡ የሚሆኑ ፡ ጻድቃን ፡ ሰባት ፡ እጅ ፡ ያበራሉ ፡ ይባላሉ ፤

፰ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ብዙኃን ፡ ሰንበታት ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ኍልቍ ፡ ለዓለም ፡ በኂሩት ፡ ወበጽድቅ ፡ ይከውኑ ፤ ጌታ ፡ ከተወለደ ፡ በኋላ ፡ በእውነት ፤ በቸርነት ፡ የሚደረጉ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ የትውልድ ፡ ሱባዔ ፡ ይሆናሉ ፤ አንድም ፡ ወእምድኅረዝ ፡ ትከውን ፡ ካልዕት ፡ ሰንበት ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እውነት ፡ ምሥጢር ፡ የሚገለጽባት ፡ ሁለተኛ ፡ የምት ሆን ፡ ስምንተኛ ፡ የዘመን ፡ ሱባዔ ፡ ይሆናል ፤ ጌታ ፡ የተወለደ ፡ በ፭ሺህ ፡ ከ፭፻ ዘመን ፡ ነው ፤ ሰባቱን ፡ መቶ ፡ አንድ ፡ ሱባዔ ፤ ሰባቱን ፡ መቶ ፡ አንድ ፡ ሱባዔ ፤ እያልህ ፡ ቍጠር ፡ ከሺሑ ፡ ፫፻ ከሺሑ ፡ ፫፻ ፤ ዘመን ፡ እየነሣህ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሱባዔ ፡ አድርገው ፤ ፭ሺህ ፡ ከ፭፻ ዘመን ፡ ፯ ሱባዔ ሁኖ ፡ ፲፻ ፡ ይተርፋል ፤ ሕፁፁን ፡ ፫ መልቶ ፡ ፰ ፡ ሱባዔ ፡ እለ ፤ ወይትወሀብ ፡ ሰይፍ ፤ ለሐዋርያት ፡ ሥልጣን ፡ ይሰጣል ፤ እምእለ ፡ ይገፍዑ ፤ ነፍሳትን ፡ በሚበድሉ ፡ በአጋንንት ፡ እውነት ፡ ፍርድ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፤ ወይትሜጠዉ ፤ አጋንንት ፡ መናፍቃን ፡ በሐዋርያት ፡ እጅ ፡ ይወድቃሉ ፤ በተፍጻሜታ ፡ ያጠርዩ ፡ አብያተ ፤ ሐዋርያት ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ይዋጃሉ ፤ ወይትሐነጽ ፡ ቤት ፤ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይሠራል ፡ ወእምድኅረዝ ፡ በሰንበት ፡ ታስዕ ፡ ስምንቱ ፡ ሱባዔ ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ በ፱ነኛው ፡ ሱባዔ ፡ እውነተኛው ፡ ምሥጢር ፡

ይገለጽባታል ፤ ሽሕ ፡ ከ፭፻ ፡ ተርፏል ፤ ያልተቆጠረ ፡ ከ፭ቱ ፡ ፻ ፡ ፩ዱን ፡ መቶ ፡ አንስቶ ፡ ከመ፪ መሪያው ፡ ከ፮ቱ ፡ ፻ ፡ ላይ ፡ ይጥ ኂል ፡ ፰ ሱባዔ ፡ ሁኖ ፡ ፴፻ ይተርፋል ከሽሑ ፡ ፫ቱን ፡ ፻ አምጥቶ ፤ ከአራት ፡ መቶ ፡ ቢጥሉት ፡ ፯፻ ፡ ይሆናል ፤ ከ፰ ሱባዔ ፡ ላይ ፡ ቢጨምሩት ፡ ፱ ሱባዔ ፡ ያለው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ዘመን ፡ ሊቃውንት ፡ ነው ፤ ወዘሎሉ ፡ ተግባረ ፡ ረሲዓን ፤ የመናፍቃን ፡ ክህደታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ፤ ለኃጕል ፡ ዓለም ፤ ኃጥዕ ፡ መናፍቅ ፡ ለጥፋት ፡ ይቈጠራል ፤ ይኄጽሩ ፡ ፍኖተ ፡ ርትዕ ፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የቀናች ሕገ፡ ወንጌልን ፡ ይመለከታል ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሰንበት ፡ ዐሥር ፡ በዐሥረኛው ፡ ሱባዔ ፡ ለዘለዓለም ፡ የሚኖር ፡ ፍጹም ፡ ፍርድ ፡ ይደረጋል ፤ ወትትገበር ፡ እምትጉሃን ፤ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ፍርድ ፡ ይደረጋል ፤ በምጽአት ፡ ፍዳ ፡ ይጸናባቸዋልና ፡ ፯፻ ፡ ተርፏል ፤ ይህ ፡ ፩ ሱባዔ ፡ ነው ፤ ከ፱ ሱባዔ ፡ ቢጨምሩት ፡ ፲ ሱባዔ ፡ ያለው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከ፯ ሽሕ ፡ ዛሬ ፡ ትርፍ ፡ ይዘናልሳ ፡ ቢሉ ፡ መጽሐፍ ፡ ትርፉን ፡ ትቶ ፡ መናገር ፡ ልማድ ፡ ነው ፤ ትርፍ ፡ ከሆነ ፡ ብሎ ፡ ተወው፤ አንድም ፡ በቢዘንም ፡ አቈጣጠር ፡ ገና ፡ ነውና ፤ ወሰማይ ፡ ዘይበቀል ፤ በመላእክት ፡ መካከል ፡ ፀንቶ ፡ የሚኖር ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰጣል ፤ ወየኀልፍ ፤ ጠፈር ፡ ያልፋል ፤ ይትረአይ ፤ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ይሰጣል ፤ ያበርሁ ፤ የሰማይ ፡ ሠራዊት ፡ ጻድቃን ፡ ፯ ፡እጅ ፡ ያበራሉ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ሰንበታት ፡ ከዐሥሩ ፡ ሱባዔ ፡ በኋላ ፡ በእውነት ፡ በቸርነት ፡ የሚገኙ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ አዝማነ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰጣሉ ፤

ወኃጢአት ፡ እምህየ ፡ ኢትትበሀል ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤

ከምጽአት ፡ በኋላ ፡ ኃጢአት ፡ ትሠራለች ፡ አትባልም ፤

፱ ፤ ወይእዜኒ ፡ እብለክሙ ፡ ደቂቅየ ፡ ወአርእየክሙ ፡ ፍናዋተ ፡ ጽድቅ ፡ ወፍናዋተ ፡ ግፍዕ ፤

አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ እውነተኛውን ፡ ሕግ ፤ አስተምራችኋለሁ ፤ የግፍ ፡ ሥራዎችንም ፡ አስተምራችኋለሁ ፤

ወአርእየክሙ ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ታእምሩ ፡ ዘይመጽእ ፤

ዳግመኛ ፡ የሚመጣባችሁን ፡ መከራ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ገልጬ ፡ አስተምራችኋለሁ ፤

፲ ፤ ወይእዜኒ ፡ ስምዑኒ ፡ ደቂቅየ ፡ ወሑሩ ፡ በፍናዋተ ፡ ጽድቅ ፤

አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ ስሙኝ ፡ በበጎ ፡ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፤

፲፩ ፤ ወኢትሑሩ ፡ በፍናዋተ ፡ ግፍዕ ፤

በግፍ ፡ ሥራዎች ፡ ጸንታችሁ ፡ አትኑሩ ፡ እላችኋለሁ ፤

እስመ ፡ ይትኀጐሉ ፡ ለዓለም ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ የሐውሩ ፡ በፍኖተ ፡ ዓመፃ ፤

በግፍ ፡ ሥራ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለዘለ ዓለም ፡ ይጠፋሉና ፤

፲፪ ፤ ዘተጽሕፈ ፡ እምሄኖክ ፡ ጸሐፊ ፡ ዝ ፡ ኵሉ ፡ ትምህርተ ፡ ጥበብ ፡ እምኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ስቡሕ ፡ ወመኰንነ ፡ ኵሉ ፡ ምድር ፤

የዓለም ፡ ሁሉ ፡ መምህር ፡ የምሆን ፤ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ክቡር ከምሆን ፡ ከእኔ ፡ ከሄኖክ ፡ የተጻፈ ፤ አንድም ፡ የዓለም ፡ ሁሉ መምህር ፡ ከሚሆን ፡ ከዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ክቡር ፡ ከሚሆን ፡ ከጌታ ተገልጾልኝ ፤ ከእኔ ፡ ከጸሐፊ ፡ ሄኖክ ፡ ተጻፈ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የጥበብ ፡ ትምህርት ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የጥበብ ፡ ትምህርት ፡ ከጸሐፊ ፡ ከእኔ ፡ ከሄኖክ ፡ የተገኘ ፤ አንድም ፡ ከጸሐፊ ፡ ከእኔ ፡ ከሄኖክ ፡ የተገኘ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የጥበብ ፡ ትምህርት ፡ ነው ፤

፲፫ ፤ ለኵሎሙ ፡ ውሉድየ ፡ እለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወለትውልድ ፡ ደኃራውያን ፡ እለ ፡ ይገብሩ ርትዐ ፡ ወሰላመ ፤

በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለሚኖሩ ፡ ለልጆቼ ፡ ሁሉ ፡ ፍቅርንና ፡ የቀና ፡ ነገርን ፡ ለሚሠሩ ፡ ኋላም ፡ ለሚወለዱ ፡ ለልጆቼ ፡ ሁሉ ፡ ትድረስ ፤

፲፬ ፤ ኢትኅዝን ፡ መንፈስክሙ ፡ በአዝማን ፡ እስመ ፡ መዋዕለ ፡ ወሀበ ቅዱስ ፡ ወዓቢይ ፡ ለኵሉ ፤

ክቡር ፡ ገናና ፡ የሚሆን ፡ ንጹሕ ጌታ ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ አዝማነ ንስሓን ፡ ሰጥቷልና ፤ ኃጢአት ፡ ሠርታችሁ ፡ ገሃነም ፡ ወርዳችሁ ፡ በአዝማኑ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ነፍሳችሁ ፡ እንዳታዝን ፡ ትሁን ፤

፲፭ ፤ ወይትነሣእ ፡ ጻድቅ ፡ እምንዋም ፤

ጻድቅ ፡ ከንዋመ ፡ ሐኬት ፡ ከንዋመ ፡ ኃጢአት ፡ ይነሣል ፤

ይትነሣእ ፡ ወየሐልፍ ፡ በፍኖተ ፡ ጽድቅ ፤

በእውነት ፡ ሥራ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤

፲፯ ፤ ወኵሉ ፡ ፍኖቱ ፡ ወምሕዋሪሁ በኂሩት ፤
ሥራው ፡ ሁሉ ፡ ዘበኂሩት ፤ በቸርነት ፡ የሆነ ፡ ነው፤ አንድም ፡ ወይትነሣእ ፡ ጻድቅ ፤ ጻድቀ ፡ ባሕርይ ፡ ክርስቶስ ፡ ከንዋመ ፡ ትዕግሥት ፡ ይነሣል፤ ወየኀልፍ ፤ እውነት ፡ ፍርድን ፡ በመፍረድ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤ ወኵሉ ፡ ፍኖቱ ፡ ወምሕዋሪሁ ፡ አነዋወሩ ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ። ዘበኂሩት ፤ በቸርነት ፡ የሆነ ፡ ነው ፡ ይባላል ፤
ወበሣህል ፡ ዘለዓለም ፡ ይሠህሉ ፤ ለጻድቅ ፤
በዘለዓለም ፡ ይቅርታ ፡ ጻድቅን ፡ ይቅር ፡ ይለዋል ፤
ወሎቱ ፡ ይሁብ ፡ ርትዐ ፡ ዘለዓለም ወይሁብ ፡ ሥልጣነ፤
በእርሱም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ የቀና ፡ ሥራን ፡ ሥልጣንንም ፡ ይሰጠዋል ፤
፲፰ ፤ ወይከውን ፡ በኂሩት ፤ ወበጽድቅ ፡ ወየሐውር ፡ ብርሃን ፡ ዘለዓለም፡ ብርሃን ፡ ጸጋ ፡ ከተሰጠ ፡ በኋላ፡ በእውነት ፡ ሥራ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤
ወኃጢአት ፡ በጽልመት ፡ ትትኀጐል ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤
በድንቁርና ፡ (ባለማወቅ) የተሠራች ፡ ኃጢአት ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ትጠፋለች ፤

ወኢትትረአይ ፡ እንከ ፡ እምይእቲ ፡ ዕለት ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤
ከዚያችም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ ትሠራለች ፡ አትባልም ፤
፲፱ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ኮነ ፡ ሄኖክ ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሄኖክ ፡ እንዲህ ሆነ ፤
ወአኀዘ ፡ ይትናገር ፡ እመጻሕፍት ፤
ኮነ ፡ ያለውን ፡ አኀዘ ፡ ብሎ ፡ አመጣው ፤ ከመጻሕፍት ፡ እየጠቀሰ ፡ ይናገር ፡ ጀመረ ፤
፲፱ ፤ ወይቤ ፡ ሄኖክ ፡ በእንተ ፡ ውሉደ ፡ ጽድቅ ፡ ወበእንተ ፡ ኅሩያን ፡ ዓለም ፤
ሄኖክ ፡ ስለ ፡ ውሉደ ፡ ጽድቅ ፡ (የሕጋውያንን ፡ ነገር )፡ ስለኅሩያን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ የደናግልንም ፡ ነገር ፤
ወበእንተ ፡ ተክለ ፡ ጽድቅ ወርትዕ ፤
ምግባር ፤ ሃይማኖት ፡ ስለሚሠሩ ፡ ልጆች ፤
እሉንተ ፡ አብለክሙ ፡ ወአየድዐክሙ ፡ ደቂቅየ ፤
ልጆቼ ፡ እነዚህን ፡ ነገሮች ፡ እነግራችኋለሁ ፡ አለ ፤
፳ ፤ አነ ፡ ውእቱ ፡ ሄኖክ ፡ ዘአስተርአየኒ ፡ እምራእየ ፡ ሰማይ ፤
በሰማይ ፡ የታየኝን ፡ ራእይ ፡ እኔ ፡ ሄኖክ ፡ እነግራችኋለሁ ፤

ወእምቃለ ፡ ቅዱሳን ፡ መላእክት ፡ አእመርኩ ፤
ከቅዱሳን ፡ መላእክት ፡ ሰምቼ ፡ ያወቅሁትን ፤
ወእምጸፍጸፈ ፡ ሰማይ ፡ ለበውኩ ፤
በጸፍጸፈ ፡ ሰማይ ፡ ልብ ፡ ያደረግሁትን ፡ እነግራችኋለሁ ፤

፳፩ ፤ ወአንዘ ፡ እንከ ፡ ይትናገር ፡ ሄኖክ ፡ እመጻሕፍት ፤
ሄኖክም ፡ ከመጻሕፍት ፡ እየጠቀሰ ፡ ይናገር ፡ ጀመር ፤
ወይቤ ፡ አነ ፡ ሳብዕ ፡ ተወለድኩ ፡
በቀዳሚት ፡ ሰንበት ፡ በመጀመሪያቱ ፡ ሱባዔ ፡ ሰባተኛ እኔ ፡ ተወለድኩ ፤ አንድም ፡ ሳብዐ ፡ ቢል ፡ ሰባተኛ ፡ ሁኜ ፡ ተወለድኩ ፤
አንድም ፡ በመጀመሪያው ፡ ሱባዔ ፡ አዳም ፤ ሴት ፤ ሄኖስ ፡ ቃይናን ፤ መላልኤል ፤ ያሬድ ፤ ሄኖክ ፤

፳፪ ፤ እስከ ፡ አመ ፡ ኮነኒ ፡ ወጽድቅ ፡ ተዐገሠ ፤
እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ እስኪፈረድ ድረስ ፡ ታገሠ ፤
ወትቀውም ፡ እምድኅሬየ ፡ በካልእት ፡ ሰንበት ፤
በሁለተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፤
ዓባይ ፡ እኪት ፤
ጽኑ ፡ ጥፋት ፡ ይሆናል ፤

፳፫ ፤ ወኮሕሉት ፡ በቁለት ፤
ተንኮል ፡ ትጸናለች ፤ ሄኖክ ፡ ብሎ ፡ ቆሚል ፤ ማቱሳላ ፤ ላሜህ ፤ ኖኅ ፤ ሴም ፡ አርፋክስድ ፤ ቃይናን ፡ ሳላ፤
ወባቲ ፡ ትከውን ፡ ፍጻሜ ፡ ቀዳሚት ፤
በሁለተኛው ፡ ሱባዔ ፡ የመጀመሪያው ፡ መቅሠፍት ፡ ይሆናል ፤
የሰው ፡ መጨረሻ ፡ ይሆናል ፤
አናቦ ፡ የመጀመሪያው ፡ መቅሠፍት ፡ መጨረሻ ፡ ይሆናል ፤

፳፬ ፤ ወባቲ ፡ ይድኅን ፡ ብእሲ፤
በሁለተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ኖኅ ፡ ይድናል ፤
ወእምድኅረ ፡ ተፈጸመ ፡ ትልሕቅ ፡ ዓመፃ ፤
ሁለተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ኃጢአት ፡ ትበዛለች ፤
ወሥርዓተ ፡ ይገብር ፡ ለኃጥአን ፤
ለሰብእ ፡ ሰናዖር ፡ ዝርወተ ፡ ልሳን ፡ ያደርጋል ፤

፳፭ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሣልስት ፡ ሰንበት ፡ በተፍጻሜታ፤
ከ፪ተኛው ፡ ሱባዔ ፡ በኋላ ፡ በ፫ተኛው ፡ ሱባዔ ፡ በመጨረሻው ፤
ይትኀረይ ፡ ብእሲ ፤
አብርሃም ፡ ይመረጣል ፤
ለተክለ ፡ ኮነኔ ፡ ጽድቅ ፤
እውነተኛ ፡ ሕግ ፡ ለመሥራት ፤
አንድም ፡ ተክለ ፡ ኮነኔ ፡ ቢል ፡ እውነተኛ ፡ ሕግ ፡ በመጠበቅ ፡

ይመረጣል ፤ ሳላ ፡ ብሎ ፡ ቁሟል ፤
ኤቦር ፤ ፋሌቅ ፤ ራግው ፤ ሴሩህ ፤
ናኮር ፤ ታራ ፤ አብርሃም ፤
ወእምድኅሬሁ ፡ ይወፅእ ፡ ተክለ ፡
ጽድቅ ፡ ወርትዕ ፡ ለዓለም ፤
ከአብርሃም ፡ በኋላ ፡ ይስሐቅ ፡
ይተካል ፤ አንድም ፡ እምኔሁ ፡
ቢል ፡ ይስሐቅ ፡ ከአብርሃም ፡
ይወለዳል ፤

፮ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በራብዕት ፡
ሰንበት ፤
ከ፫ተኛው ፡ ሱባዔ ፡ በኋላ ፡ በ፬ተ
ኛው ፤ ሱባዔ ፡
በተፍጻሜታ ፡ ራእያተ ፡ ጻድቃን ፡
ወቅዱሳን ፡ ይትረአዩ ፤
የደናግል ፤ የሕጋውያን ፡ ራእይ
ይገለጻል ፤ አብርሃም ፡ ብሎ ፡
ቁሟል ፤ ይስሐቅ ፤ ያዕቆብ ፤
ይሁዳ ፤ ፋሬስ ፤ ኤስሮም ፤
አራም ፤ አሚናዳብ ፤
ወሥርዓት ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ፤
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ሊኖር ፡
ሕገ ፡ ኦሪትን ፡ ይሠራል ፤
ወዓጸድ ፡ ይትገበር ፡ ሎሙ ፤
ደብተራ ፡ ኦሪት ፡ ይሠራል ፤

፯ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሰንበት ፡
ሐምስ ፤
አራተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ከተፈጸመ ፡
በኋላ ፡ በአምስተኛው ፡ ሱባዔ ፡
በተፍጻሜታ ፤
በመጨረሻው ፤

ይትሐነጽ ፡ ቤተ ፡ ስብሐት ፤
ቤተ ፡ መቅደስ ፤
ወመንግሥት ፡ ይትሐነጽ ፡ እስከ ፡
ለዓለም ፡
ቤተ ፡ መንግሥት ፡ እስከ ፡ ዘለዓ
ለም ፡ ሊኖር ፡ ይሠራል ፤ አሚ
ናዳብ ፡ ብሎ ፡ ቁሟል ፤ ነአሶን ፤
ሰልሞን ፤ ቡኤዝ ፤ ኢዮቤድ ፤
ዕሤይ ፤ ዳዊት ፤ ሰሎሞን ፤

፰ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሳድስት ፡
ሰንበት ፡ እለ ፡ ይከውኑ ፡ ውስቴታ ፡
ጽሉላን ፡ ኵሎሙ ፤
፭ኛው ፡ ሱባዔ ፡ ከተፈጸመ ፡
በኋላ ፡ በ፮ኛው ፡ ሱባዔ ፡ በው
ስጧ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፤
ደነቋቍርት ፡ ይሆናሉ ፤ ሰሎሞን ፡
ብሎ ፡ ቁሟል ፤ ሮብዓም ፤ አብያ ፤
አሣ ፤ ኢዮሳፍጥ ፤ ኢዮራም ፤
አካዝያስ ፤ ኢዮስያስ ፡
ወይትረሳዕ ፡ ልቦሙ ፡ ለኵሎሙ ፡
እምጥበብ ፤
ልቦናቸው ፡ ከጥበብ ፤ አንድም ፡
እምልቦሙ ፡ ጥበብ ፡ ቢል ፡ ጥበብ ፡
ከልቦናቸው ፡ ይለያል ፤
ወባቲ ፡ የዐርግ ፡ ብእሲ ፤
በስድስተኛው ፡ ሱባዔ ፡ ኤልያስ ፡
ያርጋል ፤

፰ ፤ ወበተፍጻሜታ ፡ ይውዒ ፡ ቤተ ፡
መንግሥት ፡ በእሳት ፤
ይህ ፡ የተነሣበት ፡ አይታወቅም ፤
አንድም ፡ የመንግሥት ፡ ወገን ፡
ሁሉ ፡ በኵናተ ፡ ኢዩ ፡ ይጠፋል ፤

ወባቲ ፡ ይዘረዉ ፡ ኵሉ ፡ ዘመደ ፡ ሥርው ፡ ኅሩይ ፤
የተመረጠ ፡ የመንግሥት ፡ ወገን ፡ ትውልድ ፡ ሁሉ ፡ ይበተናል ፤ ኀቶልያ ፡ አስፈጅታቸዋለችና ፤
፴ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ በሳብዕ ፡ ሰንበት ፡ ትትነሣእ ፡ ትውልድ ፡ ዕሉት ፤
ከዚህ ፡ ከ፮ተኛው ፡ ሱባዔ ፡ በኋላ ፡ በ፯ኛው ፡ ሱባዔ ፡ አሉተኛ ፤ ወንጀለኛ ፡ ትውልድ ፡ ትነሣለች ፤
ወብዙኅ ፡ ምግባራቲሃ ፤
ሥራዋ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፤
ወኵሉ ፡ ምግባራቲሃ ፡ ዕልወት ፤
ሥራዋ ፡ ብዙ ፡ ውንጀላ ፡ የሆነ ሥራዋ፡ ሁሉ ፡ ወንጀል ፡የሆነ ፤ ኢዮስያስ ፡ ብሎ ፡ ቈሚል ፤ አሜስያስ ፤ አዝያን ፤ ኢዮአታም ፤ አካዝ ፤ ሕዝቅያስ ፤ ምናሴ ፤ አሞጽ ፤ ከመጀመርያው ፡ ሱባዔ ፡ ገጠመ ፤ አሞፅ ፡ ኢዮስያስን ፡ ይወልዳል ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወእምድኅረዝ ፡ ትከውን ፡ ካልእት ፡ ሰንበት ፡ ሳምኒት ፡ ቢል ፡ በቀና ፡ ነበር ፤
፴፩ ፤ ወበተፍጻሜታ ፡ ይትኅረዩ ፡ ኅሩያን ፡ ጻድቃን ፡ እምተክለ ፡ ጽድቅ ዘለዓለም ፤
ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፤ ሕግ ፡ ከመጠበቃቸው ፡የተነሣ ፡ ደናግል ፡ ሕጋውያን ፡ በ፯ኛይቱ ሱባዔ፡በመጨረሻዋ፡ይመረጣሉ፤

እለ ፡ ይትወሀብ ፡ ሎሙ ፡ ፯ቱ፡ ምክዕቢታተ ፡ ትምህርት ፡ ለኵሉ ፡ ፍጥረተ ፡ ዚአሁ ፤
ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡ ለማስተማር ፡ ሰባት ፡ ዕጥፍ ፡ ትምህርት ፡ የሚሰጣቸው ፡ ብሎ ፡ ለደናግል ፡ ለሕጋውያን ፡ ቀጸለ፤
፴፪ ፤ እስመ ፡ መኑ ፡ ውእቱ ፡ እምኵሉ ፡ ውሉደ ፡ ሰብእ ፡ ዘይክል ሰሚዐ ፡ ቃሉ ፡ ለቅዱስ ፤
የንጹሕ ፡ የክቡር ፡ የእግዚአብሔር፡ ቃሉን ፡ መስማት ፡ የሚችል ፡ ማነው ? ማነውና ፡ እርሱ ፡ ካልገለጸለት ፡ ማለት ፡ ነው ፤
ወኢይትሀወክ ፤
የመጻሕፍትንስ ፡ ቃል ፡ ሰምቶ የማይታወክ ፡ ማነው ? ማነውና ፤
ወመኑ ፡ ዘይክል ፡ ከመ ፡ የሐሊ ፡ ሕሊናሁ ፤
አሳቡን ፡ ያስብ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ማነው ? ማነውና፤
፴፫ ፤ ወመኑ ፡ ዘይክል ፡ ነጽሮቶ ፡ ለሰማይ ፡ ወኵሉ ፡ ምግባራቲሃ ፤
ሰማይን ፡ ሥራዋንም ፡ ሁሉ ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ማየት ፡ የሚችል ፡ ማነው?
፴፬ ፤ ወምንት ፡ ውእቱ ፡ ዘይክል ፡ አእምሮ ፡ ግብረ ፡ ሰማይ ፤
በሰማይ ፡ ያለውን ፡ ፍጥረት ፡ ማወቅ ፡ የሚችል ፡ ማነው ? ማነውና ፤

ወከመ ፡ ይርአይ ፡ ነፍሶ ፤
ከነፍሱ ፡ ለይቶ ፡ ሥጋውን ፤
ወእመ ፡ አኮ ፡ መንፈሶ ፤
ከሥጋው ፡ ለይቶ ፡ ነፍሱን ፡ ማየት ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ? ማነውና ፤
ወይክል ፡ ነጊረ ፤
ይህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ነፍሴ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መናገር ፡ የሚቻለው ፡ ማነው? ማነውና ፤
ወእመ ፡ አኮ ፡ ዐሪገ ፡ ወይሬኢ ፡ ኵሎ ፡ አክናፊሆሙ ፤
ጽንፈሆሙ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ የሰማይ ፡ ዳርቻውን ፡ የመላእክት ክንፋቸውን ፡ አይቶ ፡ የሚያስባቸው ፡ ማን ፡ ነው ? ማን ፡ ነውና ፤ የሚያውቅ ፡ ማነው ? ማነውና ፤
ወይሔልዮሙ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ዘይገብር ፡ ከማሆሙ ፤
ይህስ ፡ ባይሆን ፡ እንደእነርሱ ፡ ያለ ፡ መፍጠር ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ? ማነውና ፤
፴፭ ፤ ወመኑ ፡ ውእቱ ፡ ኰሉ ፡ ብእሲ ፡ ዘይክል ፡ አእምሮተ ፤
ይህም ፡ ባይሆን ፡ እንደነርሱ ፡ ማድረግ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው?
እፎ ፡ ውእቱ ፡ ራኅባ ፡ ወኑኃ ፡ ለምድር ፤
የምድርን ፡ ስፋቷን ፤ አቈልቋይዋን ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ? ማነውና ፤

፴፮ ፤ ወስመኑ ፡ ተርእያ ፡ አምጣነ ፡ ኵሎሙ ፤
የእሊህስ ፡ መጠን ፡ ለማን ፡ ታየ? ይህን ፡ ሁሉ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው? ማነውና ፤
ወእፎመ ፡ ቦቱ ፡ ኵሉ ፡ ብእሲ ፡ ዘይክል ፡ አእምሮተ ፡ ኑኃ ፡ ለሰማይ ፤
የሰማይን ፡ አቈልቋይዋን ፡ ወርዷን ፡ የሚአውቅ ፡ ቢኖር ፡ ቦቱ ፡ በእርሱ ፡ ነው ፤
ወእፎ ፡ ውእቱ ፡ ልዕልናሃ ፡ ወዲበ ፡ ምንት ፡ ጸንዐት ፤
የሰማይ ፡ ርዝመቷን ፤ የጸናች በትም ፡ በምን ፡ ላይ ፡ እንደሆነ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ? ማነውና ፤
ወሚመጠን ፡ ውእቱ ፡ ኍልቆሙ ፡ ለከዋክብት ፤
የከከቦችም ፡ ቁጥራቸው ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደሆነ ፤
ወበአይቴ ፡ የዐርፉ ፡ ኵሎሙ ፡ ብርሃናት ፤
ፀሐይ ፡ ጨረቃ ፡ ከዋክብት ፡ በዬት ፡ እንዲያርፉ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻለው ፡ ማነው? ማነውና ፤
በምሥራቅ ፡ ወጥተው ፤ በምዕራብ ፡ ቢገቡ ፡ ቦቱ ፡ በእርሱ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፺፬

[illegible] ፡ ወይእዜኒ : ደቂቅየ ፡ እብለክሙ :
አፍቅርዋ : ለጽድቅ ፡
አሁንም : ልጆቼ ፡ እውነተኛ
ዩቱን ፡ ሕግ : ውደዷት ፡ ነቢ
ያት : እንጂ ፡ ይህን : ሁሉ :
ማየታቸው : ሕግን : ቢጠብቁ :
ነው ፡ ሕግን ፡ ውደዱ ፡
ወባቲ : ሑሩ ፡ እስመ : ፍናዊተ :
ጽድቅ : ይደሉ : ይትወከፍዎሙ ፡
በእርሷም : ጸንታችሁ : ኑሩ ፡
እላችኋለሁ ፡ የእውነት : ሥራ
ዎችን : ይቀበሏቸው : ዘንድ :
ይገባልና ፡

[illegible] ፡ ወፍናዊተ : ዐመፃ : ፍጡነ :
ይትኀጐሉ ፡
የግፍ ፡ ሥራዎች ፡ ግን :
ፈጥነው : ይጠፋሉ ፡
ወየሐጽጹ ፡
ይጠፋሉ : ያንሳሉና ፡
ወለሰብእ : እሙራን : እምትውልድ :
ይትከሠቱ : ፍናዊተ : ግፍዕ : ወሞት ፡
የሞትና ፡ የግፍዕ ፡ ሥራዎች :
ከሰው : ተለይተው : በደግነት ፡
ለታወቁ : ሰዎች ፡ ይገለጻሉ ፡
ወይርኅቁ : እምኔሆሙ : ወኢይተል
ውዎሙ ፡
ከግፍዕ : ሥራዎች : ይርቃሉ ፡
እነርሱንም : አይከተሏቸውም ፡

፫ ፡ ወይእዜኒ : ለክሙ : እብለክሙ :
ለጻድቃን ፡ ኢትሑሩ : በፍናዊተ :
እኩይ : ወግፍዕ : ወኢበፍናዊተ ፡
ሞት ፡
አሁንም ፡ ለናንተ : ለወዳጆቼ :
በግፍና ፡ በክፉ ፡ ሥራዎች ፡
ሞትን : በሚያመጡ : ሥራዎች ፡
ጸንታችሁ ፡ አትኑሩ ፡
ወኢትቅረቡ : ኀቤሆሙ : ከመ ፡
ኢትትኀጐሉ ፡
መንግሥተ : ሰማያትን : እንዳ
ታጡ : ኢትትኀጐሉ : ቢል :
እንዳትጐዱ : ወደእነርሱ : አትቅ
ረቡ : እላችኋለሁ ፡
አላ : ፍቅዱ ፡ ወኅረዩ : ለክሙ ፡
ጽድቀ : ወሕይወተ : ኅሬተ ፡
ነገር : ግን : እውነትን ፡ የተመ
ረጠች : ሕይወተ : ነፍስን : ለእና
ንተ : ፈጽማችሁ ፡ ምረጡ ፡

[illegible] ፡ ወሑሩ : በፍናዊተ : ሰላም ፡
በጽድቅ : ሥራ ፡ ጸንታችሁ : ኑሩ ፡
ወተሐይዉ ፡
ትድናላችሁ ፡
ወትዴለዉ ፡
በተድላ : በደስታውም ፡ ትዘጋ
ጃላችሁ ፡

ወትእኅዙ ፡ በሕሊና ፡ ልብክሙ ።
እኔ ፡ የነገርኋችሁን ፡ ከሰማችሁ ፡ በልቡናችሁ ፤ ዕውቀት ፡ ትይዛላችሁ ፤ ተእኅዙ ፡ ቢል ፡ ዕውቀትን ፡ ትይዙ ፡ ዘንድ ።
ሑሩ ፡ በፍኖተ ፡ ሰላም ፤ ከመ ፡ ትሕየዉ ፤
ትድኑ ፡ ዘንድ ፡ በሕግ ፡ ሥራ ፡ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፤
፭ ፡ ወኢይደምሰስ ፡ ነገርየ ፡ እምል ብክሙ ፤
ነገሬ ፡ ከልቦናችሁ ፡ አይጥፋ ፤
እስመ ፡ አአምር ፡ ከመ ፡ ያሜክርዎሙ ፡ ኃጥአን ፡ ለሰብእ ፡ ከመ ፡ ይግበሩ ፡ ጥበበ ፡ እኩየ ፤
ክፉ ፡ ጥበብን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ደጋጎች ፡ ሰዎችን ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ እንዲፈትኗዋቸው ፡ አው ቃለሁና ፤
ወኵሉ ፡ መካን ፡ ኢይትረከብ ፡ ላቲ ፤
ለኃጢአት ፡ በታ ፡ ሁሉ ፡ አይገ ኝላትም ፤
ወኵሉ ፡ መከራ ፡ ኢየሐፅፅ ፤
መከራ ፡ ሁሉ ፡ ከእርሷ ፡ አይር ቅም ፤
፮ ፡ አሌ ፡ ሎሙ ፡ ለእለ ፡ የሐንጽዋ ፡ ለዓመፃ ፡ ወለግፍዕ ፡ ወይሣርርዋ ፡ ለጕሕሉት ፤
ሐሰት ፡ ነገርን ፤ ግፍንም ፡ ተን ኰልንም ፡ አጥንተው ፡ ለሚሠ ሯት ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፤

እስመ ፡ ፍጡነ ፡ ይትነሠቱ ፡ ወአል ቦሙ ፡ ሰላም ፤
እነርሱ ፡ ፈጥነው ፡ ይጠፋሉና ፤
ፍቅር ፡ አንድነትም ፡ የላቸውምና ፤
፯ ፡ አሌ ፡ ሎሙ ፡ ለእለ ፡ የሐንጹ አብያቲሆሙ ፡ በኃጢአት ፤
የድሀ ፡ ከብት ፡ ቀምተው ፤ እን ድም ፡ ደመወዝ ፡ ቀምተው ፤ ቤታ ቸውን ፡ ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላ ቸው ፤
እስመ ፡ እምኵሉ ፡ መሠረቶሙ ፡ ይትነሠቱ ፤
ከሥር ፡ መሠረታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋሉና ፤
ወበሰይፍ ፡ ይወድቁ ፤
በሰይፍም ፡ ተቀራድደው ፡ ያል ቃሉና ፤
ወእለ ፡ ያጠርይዋ ፡ ለወርቅ ፡ ወለብ ሩር ፡ በኰነኔ ፡ ፍጡነ ፡ ይትኀጐሉ ፤
ወርቅን ፡ ብርን ፡ የሚሰበስቧት ፡ ሰዎች ፡ በፍርዱ ፡ ፈጥነው ፡ ይጠ ፋሉና ፤
፰ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ አብዕልት ፤
እናንተ ፡ ባለጸጎች ፡ ወዮላችሁ ፤
እስመ ፡ ዲበ ፡ ብዕልክሙ ፡ ተወከ ልክሙ ፤
በባለጸግነታችሁ ፡ ላይ ፡ ታምና ችኋልና ፤
ወእምነ ፡ ብዕልክሙ ፡ ትወጽኡ ፤
ከባለጸግነታችሁም ፡ ትለያላችሁና ፡
እናንተ ፡ ባለጸጎች ፡ ወዮላችሁ ፤

እስመ ፡ ለልዑል ፡ ኢተዘከርክ
ምዎ ፡ በመዋዕለ ፡ ብዕልክሙ ፡፡
በብዕላችሁ ፡ (በባለጠግነታችሁ)
ወራት ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔርን ፡
አላሰባችሁትምና፡፡ አንድም ፡ በመ
ዋዕለ ፡ ብዕልክሙ ፡ ገበርክምዎ ፡
ለጽርፈት ፡ ብለህ ፡ ወደታች ፡
አንብብ ፡፡
ወገበርክምዋ ፡ ለፅርፈት ፡ ወለዓመፃ ፡፡
እናንተስ ፡ ስድብን ፡ በደልንም ፡
ሠራችኋት ፡፡
ወድልዋነ ፡ ኮንክሙ ፡ ለዕለተ ፡
ክዕወተ ፡ ደም ፡፡
ደም ፡ ለሚፈስስባት ፡
ወለዕለተ ፡ ጽልመት ፡ ወለዕለተ ፡
ኰነኔ ፡ ዓባይ ፡፡
ጨለማም ፡ ለሚደረግባት ፡፡ ጽኑ
ፍርድም ፡ ለሚፈረድባት ፡ ለታ
ላቋ ፡ ለዕለተ ፡ ምጽአት ፡ የተዘ
ጋጃችሁ ፡ ሆናችሁ ፡፡
፲ ፡ ወከመዝ ፡ እብል ፡ አነ ፡ ወዐየ
ድአክሙ ፡ ከመ ፡ ይገፈትዐክሙ ፡
ዘፈጠረክሙ ፡፡
የፈጠራችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲያጠፋችሁ ፡፡
ወዲበ ፡ ድቀትክሙ ፡ ከመ ፡ ኢይከ
ውን ፡ ምሕረት ፡፡
በናንተም ፡ ጥፋት ፡ ላይ ፡ ይቅ
ርታው ፡ እንዳይደረግላችሁ ፡ እን
ዲህ ፡ ብዬ ፡ እነግራችኋለሁ ፡፡

፲፩ ፡ ወፈጣሪክሙ ፡ ይትፌሣሕ ፡
በንጕልክሙ ፡፡
እናንተንም ፡ የፈጠረ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በእናንተ ፡ ጥፋት ፡ ደስ
ይለዋል ፡፡
ወጻድቃነ ፡ ዚአክሙ ፡፡
አበ ፡ አበ ፡ የምትሏቸው ፡ መም
ህሮቻችሁ ፡፡
ይከውኑ ፡ በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡
ፅዕለተ ፡ ለኃጥአን ፡ ወለረሲዓን ፡፡
ይከውኑ ፡ ጽሉአነም ፡ ይላል ፡፡ በዕ
ለተ ፡ ምጽአት ፡ ኃጥአን ፡፡ አጋን
ንት፡ ለሚሰድቡት ፡ ስድብ ፡ ይሆ
ናሉ ፡፡

## ጉባኤ

፲፪ ፡ መኑ ፡ ይሁብኒ ፡ ከመ ፡ ይኩና፡
አዕይንትየ ፡ ደመናተ ፡ ማይ ፡፡
ዓይኖቼ ፡ ውሀን ፡ የቋጠሩ ፡
ደመናዎች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡
ማን ፡ በሰጠኝ ? ለነቢያት ፡
ብዝኃ ፡ አንብዕ ፡ ተሰጥቷቸው፡
ሳለ ፡ መመኘት ፡ ልማዳቸው ፡
ነው ፡፡ ኤርምያስ ፡ መኑ ፡ ይሁ
በኒ ፡ ማየ ፡ ስርእስየ ፡፡ ወፈል
ፌለ ፡ አንብዕ ፡ ለአዕይንትየ ፡
ብሏል ፡፡ ኢሳይያስም ፡ መኑ ፡
ይሁብኒ ፡ ኀለተ ፡ ወሣዕረ ፡
ከመ ፡ አውዕዮ ፡ በእሳት ፡
ብሏል ፡፡ እዚህም ፡ እንዲህ ፡
አለ ፡፡

ወእብለ ፡ ዲቤክሙ ፡ ወእክዐው ፡
እንብዕየ ፤ ከመ ፡ ደመና ፡ ማይ ፤
ዝናም ፡ እንደ ፡ ቋጠረ ፡ ደመና
ዕንባዬን ፤ አፈስስ ፡ ዘንድ ፤
ወአዕርፍ ፡ እምኀዘነ ፤ ልብየ ፤
አልቅሼ ፡ አልቅሼ ፤ ወጥቶልኝ ፡
ከልቦናዬ ፤ ኃዘን ፤ አርፍ ፡ ዘንድ ፤
ለዓይናቼ ፡ እንባን ፡ ማን ፡ በሰ
ጠኝ ፤ ነበር ?
፲፫ ፤ መኑ ፡ ወሀበክሙ ፡ ከመ ፡
ትግበሩ ፤ ዕልወ ፡ ወእከየ ፤
ጥል ፤ ክርክርን ፤ ታደርጉ ፤
ዘንድ ፤ ማን ፡ አስተማራችሁ ?
ወይረክበክሙ ፡ ለኃጥአን ፡ ኵነኔ ፤
ኃጥአን ፡ እናንተን ፤ ቁርጥ ፡
ፍርድ ፤ ያገኛችኋል ፤
፲፬ ፤ ኢትፍርሁ ፡ ጻድቃን ፡ እምኃ
ጥአን ፤
ወዲዶቼ ፡ ጻድቃን ፡ ከኃጥአን ፡
የተነሣ ፡ አትፍሩ ፤ በሥጋ ፡
መከራ ፡ ያጸኑብናል ፤ ብላችሁ ፤
አንድም ፡ በኃጥአን ፤ በነፍስ ፤
የመጣውን ፡ መከራ ፡ አይታችሁ ፡
አትፍሩ ፤
እስመ ፡ ካዕበ ፤ ያገብኦሙ ፤ እግዚ
አብሔር ፡ ውስተ ፡ እዴክሙ ፡ ከመ
ትግበሩ ፡ ኵነኔ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ በከመ
ፈቀድክሙ ፡
እንደ ፡ ወደዳችሁ ፡ በእነርሱ ፤
ላይ ፡ ፍርድን ፡ ታደርጉባቸው
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፤ ዳግመኛ
በእጃችሁ ፤ ይጥላቸዋልና ፤
፲፭ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ታወ
ግዙ ፡ ግዘታተ ፡ ከመ ፡ ኢትፍትሑ ፤
በራሳችሁ ፡ እንዳትፈርዱ ፡ ሆና
ችሁ ፡ ሰውን ፡ ከእግዚአብሔር ፡
የምትለዩ ፤ አንድም ፡ እንዳትፈቱ ፡
በማይገባ ፡ የምታወግዙ ፡ ወዮ
ላችሁ ፤ ወግዘትሰ ፡ ርኁቅ ፡
እምዘልማዱ ፡ ርትዕ[፩] ፡ እንዲል ፤
ወፈውስ ፤ ርኁቅ ፤ እምኔክሙ ፡
በእንተ ፡ ኃጢአተ ፡ ዚአክሙ ፤
ስለ ፤ ኃጢአታችሁም ፡ ድኅነተ ፡
ነፍስ ፡ ከእናንተ ፡ የራቀ ፡ ነው ፤
[illegible] ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትፌ
ድዩ ፡ እኩየ ፤ ለቢጽክሙ ፤
ባልንጀራችሁ ፡ በጎ ፡ ቢያደርግላ
ችሁ ፡ ክፉ ፡ ለምታደርጉ ፤ አን
ድም ፡ ክፉ ፤ ቢያደርጉባችሁ ፡
ቅሉ ፡ ክፉ ፡ ለምትመልሱ ፡ ወዮ
ላችሁ ፤
እስመ ፤ ትትፈደዩ ፡ በከመ ፤ ምግ
ባሪክሙ ፤
እንደ ፡ ሥራችሁ ፡ መጠን ፡
ፍዳውን ፡ ትቀበላላችሁና ፤
፲፯ ፤ አሌ ፤ ለክሙ ፡ ለሰማዕተ ፡
ሐሰት ፡ ወለእለ ፡ ትደለውዋ ፡ ለዓመፃ ፤
ሐሰትን ፡ ለምትመሰክሩ ፤ ዓመ
ፃን ፡ ለምትስማሙት ፡ ለምትሠ
ሯት ፡ ወዮላችሁ ፤

---

፩ ፤ ፶. አበው ምዕ. ፪ቍ፩-፲፯

እስመ ፡ ፍጡነ ፡ ትትኀጐሉ ።
በሠራችሁት ፡ ሥራ ፡ ፈጥናችሁ ፡
ትጠፋላችሁና ።
[illegible] ። አሌ ፡ ለክሙ ፡ ለኃጥአን ፡
እስመ ፡ ለጻድቃን ፡ ትሰድድዎሙ ።
ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ አስወጥታችሁ ፡
ትሰድዷቸዋላችሁና ፡ እናንተ ፡ ኀጥ
አን ፡ ወዮላችሁ ።
እስመ ፡ አንትሙ ፡ ትትሜጠዉ ፡
ወትሰደዱ ፡ እምዓመፃ ።
ኃጢአት ፡ የምትሠሩ ፡ እናንተ ፡
ከሠራችሁት ፡ ግፍ ፡ የተነሣ ።
ከመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ትሰደዳ
ላችሁ ፡ ለእናንተ ፡ ለኀጥአን ፡
ወዮላችሁ ።
ወይጸንዕ ፡ በላዕሌክሙ ፡ አርዑተ ፡
ዚአሆሙ ።
የጻድቃን ፡ ሥልጣን ፡ በእናንተ
በኃጥአን ፡ ይጸናል ።
፲፰ ። ተሰፈዉ ፡ ጻድቃን ፡ እስመ ፡
ፍጡነ ፡ ይትኀጐሉ ፡ ኃጥአን ፡ እም
ቅድሜክሙ ።
ጻድቃን ፡ ጠላቶቻችሁ ፡ ኃጥአን ፡
ከፊታችሁ ፡ ፈጥነው ፡ እንዲጠፉ ፡
እመኑ ።
ወሥልጣን ፡ ይከውን ፡ ለክሙ ፡
ዲቤሆሙ ፡ በከመ ፡ ፈቀድክሙ ።
ሥልጣንም ፡ በእነርሱ ፡ እንዲደ
ረግ ፡ ወዳጆቼ ፡ ጻድቃን ፡ ይህ
ንን ፡ ተስፋ ፡ አድርጉ ።

፳ ። ወበዕለተ ፡ ምንዳቤሆሙ ፡ ለኃ
ጥአን ፡ ይትሌዐሉ ።
ኀጥአን ፡ መከራ ፡ በሚቀበሉበት ፡
ቀን ፡ ጻድቃን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
ይላሉ ።
ወይትነሥኡ ፡ ከመ ፡ አንስርት ፡
ዕጐሊ ፡ ዚአክሙ ።
ዕጓሊ ፡ ዚአሆሙ ፡ ሲል ፡ ነው ።
ጻድቃን ፡ ልጆቻቸው ፡ በኃጥአን
ላይ ፡ በጠላትነት ፡ ይነሣሉ ።
አንድም ፡ ፈጥነው ፡ ይሸሻሉ ።
፳፩ ። ወፈድፋደ ፡ እምነ ፡ አውስት ፡
ይከውን ፡ ምጽላልክሙ ።
ይልቁንም ፡ ማደሪያችሁ ፡ ከጥ
ንብ ፡ እንሣ ፡ አሞራ ፡ ይርቃል ።
ወተዐርጉ ፡ ወትበውኡ ።
ወደ ፡ ተራራ ፡ ትወጣላችሁ ፡
በንድለታተ ፡ ምድር ።
በዋሻ ። በፍርኩታ ። ትገባላችሁ ።
ወበንቅዓታተ ፡ ኰኵሕ ፡ ለዓለም ፡
ከመ ፡ ግሄ ፡ እምቅድመ ፡ ዓማፅያን ።
ከአመፀኞች ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡
እንደ ፡ ሽኮኮ ፡ በገደል ፡ ተጠግ
ታችሁ ፡ ለዘለዓለም ፡ ትኖራላችሁ ።
፳፪ ። ወይገኢሉ ፡ ዲቤክሙ ።
ጽኑ ፡ ኃዘን ። ቅልቅል ፡ ኃዘን ፡
ያዝናሉ ።
ወአንትሙ ፡ ኢትከውኑ ፡ ከማሆሙ ።
እናንተ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ አት
ሆኑም ።

አላ ፡ ለማዕተ ፡ ይከውን ፡ ዲቤክሙ ፡ ዝንቱ ፡፡
ይህ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ በእናንተ ፡ ምስክር ፡ ይሆንባችኋል ፡ እንጂ ፡ ከመ ፡ ሱቱፋነ ፡ ኮንክሙ ፡ ለኃጥአን ፡ ከኃጥአንም ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆናችሁ ፡፡
ወይበክዩ ፡ ከመ ፡ ጺዴኔታት ፡፡
እንደ ፡ ሄለይ ፡ ቃላቸውን ፡ አቅጥ ነው ፡ ያለቅሳሉ ፡፡
፫ ፡ ወአንትሙሰ ፡ ኢትፍርሁ ፡ እለ ሐመምክሙ ፡ እስመ ፡ ፈውስ ፡ ይከውነክሙ ፡፡
መከራ ፡ የምትቀበሉ ፡ ጻድቃን እናንተ ፡ ግን ፡ አትፍሩ ፡ መከራው ፡ ለእናንተ ፡ ድኅነት ፡ ይሆንላችኋልና ፡፡
ወብርሃን ፡ ብሩህ ፡ ያበርህ ፡ ለክሙ ፡፡
ብርሃን ፡ ጸጋ ፡ ያበራላችኋል ፡፡
ወቃለ ፡ ዕረፍት ፡ ትሰምዑ ፡ እምሰማይ ፡፡
ንዑ ፡ ኅቤየ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ኑ የሚል ፡ ቃል ፡ ትሰማላችሁ ፡፡
፬ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ ኃጥአን ፡ እናንተ ፡ ክፉዎች ፡ ኃጥአን ፡ ወዮላችሁ ፡፡
እስመ ፡ ብዕልክሙ ፡ ያመስለክሙ ፡ ጻድቃነ ፡፡
ባለጠግነታችሁ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ ያስመስላችኋልና ፡፡
ወልብክሙ ፡ ይዛለፈክሙ ፡ ከመ ፡ ኃጥአን ፡ አንትሙ ፡፡
ልቡናችሁ ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ በደለኞች ፡ እንደሆናችሁ ፡ ይዘልፋችኋል ፡(ይወቅሳችኋል)፡፡
፭ ፡ ወዝንቱ ፡ ነገር ፡ ይከውን ፡ ዲቤክሙ ፡ ለማዕተ ፡ ለተዝካረ ፡ እከያት ፡፡
ይህም ፡ ነገር ፡ ለኃጢአታችሁ ፡ ለክፋታችሁ ፡ መታሰቢያ ፡ ምስክር ፡ ይሆናል ፡፡
፮ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትበልዑ ፡ ስብሐ ፡ ሥርናይ ፡፡
ሕፅበ ፡ (ልጦ ፡ ጉርዶ) ፡ የወጣውን ፡ ፍሬያማውን ፡ ስንዴ ፡ የምትበሉ ፡ ጸም ፡ ገድፋችሁ ፡ የድህ ፡ ከብት ፡ ቀምታችሁ ፡ ያነን ፡ በልታችሁ ፡ ኃጢአት ፡ ለምትሠሩ ፡ ወዮላችሁ ፡፡
ወትሰትዩ ፡ ኃይለ ፡ ሥርወ ፡ ነቅዕ ፡ ነቅዕ ፡ ንህብ ፡ ሥርው ፡ ማር ፡ ኃይል ፡ ጠጅ ፡ ነው ፡ ከንብ ፡ የተገኘውን ፡ ማሩን ፡ ጠጅ ፡ ጥላችሁ ፡ የምትጠጡ ፡ አንድም ፡ ነቅዕ ፡ ላም ፡ ሥርው ፡ ጡት ፡ ኃይል ፡ ወተት ፡ ነው ፡ ከላም ፡ ጡት ፡ የተገኘውን ፡ ወተት ፡ የምትጠጡ ፡ ጠጥታችሁ ፡ ኃጢአት ፡ ለምትሠሩ ፡፡

ወትከይድዎሙ ፡ ለትሑታን ፡ በኃይልክሙ ፡
ነዳያን ፡ ጻድቃንን ፤ በኃይላችሁ ፡ የምትረጋግጧቸው ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችሁ ።

፮ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትሰትዩ ፡ ማየ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
ያገዝፋልና ፤ ዝሙት ፡ ያጸናልና ፡ ብላችሁ ፤ ጸም ፡ ገድፋችሁ ፡ ያነን ፡ ጠጥታችሁ ፡ ሁልጊዜ ፡ ኃጢአት ፡ ለምትሠሩ ፡ ወዮላችሁ ።
እስመ ፡ ፍጡነ ፤ ትትፌደዩ ፤ ወትትዌድኡ ።
የኃጢአታችሁን ፡ ፍዳ ፡ ፈጥናችሁ ፡ ትቀበላላችሁ ፤ ትፈጽማላችሁና ።
ወትየብሱ ።
ትጠፋላችሁ ።
እስመ ፡ ሐደግሙ ፡ ነቅዓ ፡ ሕይወት ።
ነቅዓ ፡ ሕይወት ፡ ሕግን ፤ ትታችኋልና ።

፯ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትገብሩ ፡ ዓመፃ ፤ ወጕኅሉተ ፡ ወጽርፈተ ።
ስድብን ፤ ተንኮልን ፤ በደልን ፤ ለምትሠሩ ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
ወዝንቱ ፡ ተዝካረ ፤ ይከውን ፡ ዲቤክሙ ፡ ለእከይ ።
ይህም ፤ በእናንተ ፡ የክፋታችሁ መታሰቢያ ፡ ይሆናል ።

፰ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ ኃያላን ፡ እለ ፡ በኃይል ፤ ትከርዕዎ ፡ ለጻድቅ ።
ደጉን ፤ ሰው ፤ በኃይላችሁ ፡ ራስ ፡ ራሱን ፤ ለምትቀጠቅጡት ፡ ለእናንተ ፡ ለኃይለኞች ፡ ወዮላችሁ ።
እስመ ፡ ትመጽእ ፡ ዕለተ ፡ ኀጕልክሙ ።
የምትጠፉበት ፡ ቀን ፡ ትመጣለችና ።

፱ ፤ ወበእማንቱ ፤ መዋዕል ፤ ይመጽኣ ፡ ለጻድቃን ፡ መዋዕል ፡ ብዙኃት ወኄራት ፡ በዕለተ ፡ ኰነኔ ፡ ዚአክሙ ።
በእነዚያ ፡ ወራቶች ፡ እናንተ ፡ መከራ ፤ በምትቀበሉበት ፡ ቀን ፤ ለጻድቃን ፡ ብዙ ፡ በጎ ፡ ወራቶች ፤ ይመጣሉ ።

## ምዕራፍ ፺፯

፩ ፤ ተአመኑ ፡ ጻድቃን ፡ እስመ ፡ ለጽዕለት ፡ ይከውኑ ፡ ኃጥአን ።
ጻድቃን ፡ ኃጥአን ፡ ለስድብ ፡ እንዲሆኑ ፤ እመኑ ።
ወይትኀጐሉ ፡ በዕለተ ፡ ዓመፃ ።
የኃጢአታቸውን ፡ ፍዳ ፡ በሚቀበሉበት ፡ ቀን ፤ ለስድብ ፡ እንዲሆኑ ፡ እመኑ ።

፪ ፤ እሙረ ፡ ይከውን ፤ ለክሙ ።
ጻድቃን ፡ ይህ ፤ ለእናንተ ፤ በደግነታችሁ ፡ በምሕረት ፤ የታወቀ ፡ ይሆናል ።
እስመ ፡ ልዑል ፡ ይዜክር ፡ ኀጕለክሙ ።
እግዚአብሔር ፡ የእናንተን ፡ ጥፋት ፡ ያስባልና ፡

ወይትፌሥሑ ፡ መላእክት ፡ ዲበ ፡ ኃጕለ ፡ ዚአክሙ ።
በሰማይም ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡ በእናንተ ፡ ጥፋት ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋልና ፡ ይህ ፡ በደግነታችሁ ፡ የታወቀ፡ ይሆንላችኋል ።
፫ ፡ ምንተ ፡ ትግበሩ ፡ ሀለወክሙ ፡ ኃጥአን ፤
ኃጥአን ፡ ምን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ?
ወአይቴ ፡ ትጐይዩ ፡ በይእቲ፡ ዕለት ፡ እንተ ፡ ኮነኔ ፤
ፍርድ ፡ በሚሰጥባት ፡ በዚያች ፡ ቀንስ ፡ ወዴት ፡ ትሸሻላችሁ ?
ሶበ ፡ ትሰምዑ ፡ ቃለ ፡ ጸሎቶሙ ፡ ለጻድቃን ፤
የጻድቃንን ፤ የጸሎታቸውን ፡ ዋጋ፡ ንዑ ፡ ንቤየ ፡ ሲላቸው ፡ በምትሰሙበት ፡ ጊዜ፡ ወዴት ፡ ትሸሻላችሁ ?
ወአንትሙ ፡ ኢትከውኑ ፡ ከማሆሙ ፡ አላ ፡ ሰማዕተ ፡ ይከውን ፡ ዲቢክሙ ፡ ዝንቱ ፡ ነገር ፤
ይህ፡ መከራው ፡ ምስክር ፡ የሚሆንባችሁ ፡ ኃጥአን ፡ እንደ ፡ እነርሳቸው ፡ አትሆኑም ፤ አንድም ፡ አላ ፡ ሰማዕተ ፡ ይከውን ፡ ዲቤክሙ ፤ ይህ ፡ ኃጢአቱ ፡ ምስክር ፡ ይሆንባችኋል ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ጻድቃን ፡ አትሆኑም ፤

እስመ ፡ ሱቱፋነ ፡ ከንክሙ ፡ ለኃጥአን ፤
አኩሌቶቹ ፡ ኃጥአን ፡ እንደ ፡ አኩሌቶቹ ፡ ኃጥአን ፡ ሆናችሁ ይላቸዋል ፤ በመከራው ፡ ተባባሪዎች ፡ ሆናችሁ ፤
፬ ፡ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ትበጽሕ ፡ ጸሎቶሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፤
በእነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የቅዱሳን ፡ ልመናቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር፡ ትደርሳለች ፡
ወለክሙ ፡ ይበጽሕ ፡ መዋዕለ ፡ ኮንኔክሙ ፤
በእናንተ ፡ ግን ፡ የሚፈረድባችሁ፡ ወራት ፡ ይደርስባችኋል ፤
፭ ፡ ወይትነበብ ፡ ኵሉ ፡ ነገረ ፡ ዓመፃክሙ ፡ ቅድመ ፡ ዓቢይ ፡ ወቅዱስ ፤
በግፋችሁ፡ የሠራችሁት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በከበረና ፡ በገነነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይነበባል ፤
ወይትኀፈር ፡ ገጽክሙ ፤ ወይትገደፍ ፡ ኵሉ፡ ተግባርክሙ ፡ ዘጸንዐ ፡ በዓመፃ፤
ፊታችሁም ፡ በመከራው ፡ ያፍራል ፤ በግፍ ፡ የጸና ፡ ሥራችሁም ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ፤
፮ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ ኃጥአን ፡ እለ ፡ ማእከለ ፡ ባሕር ፡ ወዲበ ፡ የብስ ፤
በባሕርና ፡ በደሴት ፡ የምትኖሩ ወዮላችሁ ፤ በደሴት ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ይታበያሉና ፤

እለ ፡ ዝክሮሙ ፡ እኩይ ፡ ዲቤክሙ ፡
ክፉ ፡ ስም ፡ አጠራራቸው ፡ በእና
ንተ ፡ ላይ ፡ የሚሆን ፡ ይህ ፡
ሰው ፡ ፈርያን ፡ ነው ፡ ሰናክ
ሬምም ፡ ነው ፡ ይላሉ ፡
፯ ፡ እሉ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ታጠርዩ
ብሩረ ፡ ወወርቀ ፡ ዘኢኮነ ፡ በጽድቅ ፡
ስርቃችሁ ፡ ቀምታችሁ ፡ ገንዘብ
የምታጠራቅሙ ፡ ወዮላችሁ ፡
ወትብሉ ፡ ብዕልነ ፡ ብዕለ ፡ ወኮነ ፡
ለነ ፡ ንዋይ ፡
ባለ ፡ ጸግነትን ፡ አገኘን ፡ ገን
ዘቡም ፡ በዛልን ፡
ወአጥረይነ ፡ ኵሉ ፡ ዘፈቀድነ ፡
የወደድነውንም ፡ ሁሉ ፡ ገዛን ፡
የምትሉ ፡ ሰዎች ፡ ለናንተ ፡
ወዮላችሁ ፡
፰ ፡ ወይእዜኒ ፡ ንግበር ፡ ዘሐለይነ ፡
አሁንም ፡ ያሰብነውን ፡ ሁሉ ፡
እናድርግ ፡ ለምትሉ ፡ ወዮላችሁ ፡
እስመ ፡ ብሩረ ፡ አስተጋባእነ ፡ ወመ
ላእነ ፡ መዛግብቲነ ፡
ብሩን ፡ ሰብስበናልና ፡ በሳጥኖቻ
ችንም ፡ መልተናልና ፡
ወከመ ፡ ማይ ፡ ብዙኅ ፡ ኀረስተ ፡
አብያቲነ ፡
የቤታችን ፡ አራሹ ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡
ብዙ ፡ ነውና ፡ ያሰብነውን ፡ እናድ
ርግ ፡ ትላላችሁ ፡

፱ ፡ ወከመ ፡ ማይ ፡ ይውኅዝ ፡
ሐሰትክሙ ፡
በሐሰት ፡ ያጠራቀማችሁት ፡ ከብ
ታችሁ ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡ ይፈስ
ሳል ፡
እስመ ፡ ኢይነብር ፡ ለክሙ ፡ ብዕ
ልክሙ ፡ አላ ፡ ፍጡነ ፡ የዐርግ ፡
እምኔክሙ ፡
ከእናንተ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጠፋል ፡
እንጂ ፡ ባለጠግነት ፡ አይረባች
ሁምና ፡ ሐሰታችሁ ፡ እንደ ፡
ውሀ ፡ ይበዛል ፡
፲ ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ በዓመፃ ፡ አጥ
ረይክሙ ፡
ይህን ፡ ሁሉ ፡ በግፍ ፡ ሰብስባ
ችሁታልና ፡
ወአንትሙሰ ፡ ለመርገም ፡ ዓቢይ ፡
ትትወሀቡ ፡
እናንተ ፡ ግን ፡ ለጽኑ ፡ ጥፋት ፡
ትሰጣላችሁ ፡
፲፩ ፡ ወይእዜኒ ፡ አነ ፡ እምሕል ፡
ለክሙ ፡ ለጠቢባን ፡ ወለአብዳን ፡
አሁንም ፡ እኔ ፡ ለብልሆችና ፡
ለሰነፎች ፡ እምልላችኋለሁ ፡ እና
ገራችኋለሁ ፡ ጠቢባን ፡ አላቸው ፡
ገንዘብ ፡ ያጠራቅማሉና ፡ አብዳን ፡
አላቸው ፡ ሳይሰጡ ፡ ሳይመጸ
ውቱ ፡ ይሞታሉና ፡

እስመ ፡ ብዙኃ ፡ ትሬእዩ ፡ በዲበ ፡ ምድር ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ ታያላችሁና ፤
፲፪ ፡ እስመ ፡ ስነ ፡ ትወድዩ ፡ ላዕሌክሙ ፡ አንትሙ ፡ ዕደው ፡ ፈድፋደ እምአንስት ፤
እናንተ ፡ ወንዶች ፡ ከሴቶች ፡ ይልቅ ፡ ጌጥ ፡ ታጌጣላችሁ ፤
ስለሆነም ፡ ብዙ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ታደርጋላችሁና ፤
ወኅብረ ፡ ፈድፋደ ፡ እምድንግል ፡
በመንግል ፤ በጌጥ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ከድንግሊቱ ፡ ይልቅ ፡ ብዙ ፡ መልክ ፡ ያለው ፡ በጌጥ ፡ ላይ ፡ ጌጥ ፡ ታጌጣለችሁና፤ አንድም ፡ በመንገለ ፡ አንስት ፡ ይላል ፤ በሴቶች ፡ ዘንድ ፡ አጊጣችሁ ፡ አምራችሁ ፡ ትታዩ ፡ ዘንድ ፡ ታጌጣላችሁና፤
፲፫ ፡ በመንግሥት ፤
በመንግሥት ፡ ያላችሁ ፡ ይመስላችኋልና ፤
ወበዕበይ ፡ ወበሥልጣን ፤
በገናንነት ፡ በሥልጣን ፡ ያላችሁ ይመስላችኋልና፤
ወበብሩር ፡ ወወርቅ ፡ ወሜላት ፡ ወክብር ፤
በወርቅና ፡ በብር ፡ በንጭ ፡ ሐርም ፡ የከበርን ፡ ይመስላችኋልና ፤
፲፬ ፡ ወመባልዕት ፡ ከመ ፡ ማይ ይትከዓዉ ፤
መብሎችም ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ በዝተው ፡ በፊታችሁ ፡ ይቀርባሉ ፤
ወበእንተዝ ፡ ትምህርት ፡ ወጥበብ ፡ አልበሙ ፤
ስለዚህም ፡ በዝተው ፡ ስለቀረቡ ፡ ትምህርት ፤ ጥበብ ፤ የላቸውም፤
፲፭ ፡ ወቦቱ ፡ ይትኀጐሉ ፡ ኅቡረ ፡ ምስለ ፡ ንዋያቲሆሙ ፡ ወምስለ ፡ ኵሉ ፡ ስብሐቶሙ ፡ ወክብሮሙ ፤
መባልዕት ፡ በዝተው ፡ ስለቀረቡ ፤ ጥበብ ፤ ትምህርት ፡ ስለሌላቸው፡ ከገንዘባቸው ፡ ከክብራቸውና ፡ ከጌትነታቸው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡ ይጠፋሉ ፤
፲፮ ፡ ወበጽእለት ፡ ወበንጼት፤
በጽዕለተ ፡ ነፍስ ፡ (በስድብ) ፡ በንጼተ ፡ ነፍስ ፡ ሲሆኑ ፤
ወበቀትለ ፡ ነፍስ ፤
በቀትለ ፡ ነፍስ ፡ ወበቀል ፡ ቢል ፤ በጽኑ ፡ በቀልም ፡ ሆነው ፡ሲኖሩ፤
ወበንጼት ፡ ዓቢይ ፤
በፍጹም ፡ ንጼተ ፡ ነፍስ ፡ ሲኖሩ፤

ትትወደይ ፡ መንፈሰሙ ፡ ውስተ ፡
እቶን ፡ እሳት ፡፡
ነፍሳቸው ፡ በገሃነም ፡ ትወድ
ቃለች ፡፡

፲፮ ፡ መሐልኩ ፡ ለክሙ ፡ ኃጥአን
ከመ ፡ ኢኮነ ፡ ደብር ፡ ገብረ ፡
ተራራ ፡ በባሕርዩ ፡ ተገኘ ፡
እንዳልነበረ ፡ ወኢይከውን ፡ እን
ግዲህም ፡ መገዛት ፡ እንደሌለ
በት ፡ ምዬ ፡ እነግራችኋለሁ ፡
ወኢወግር ፡ ለብእሲት አመተ ፡
ኮረብታም፡ ለሴት ፡ ተገኘ ፡ እን
ዳይደለች ፡ ምዬ ፡ እነግራችኋ
ለሁ ፡

፲፯ ፡ ከመዝ ፡ ኃጢአትኒ ፡ ኢተፈ
ነወት ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡
ተራራ ፡ ኮረብታ ፡ በባሕርያ
ቸው ፡ መገዛት ፡ እንደሌለባቸው፡
ኃጢአትም ፡ የባሕርይ ፡ ሁና ፡
አልተፈጠረችም ፡
አላ ፡ሰብእ ፡ እምርእሰሙ ፡ ፈጠርዋ፡
አዳምና ፡ሔዋንም ፡ ከልቦናቸው፡
አንቅተው ፡ ሠሯት ፡ እንጂ ፡
ወለመርገም ፡ ዓቢይ ፡ ይከውኑ ፡ እለ
ገብርዋ ፡
አዳምና ፡ ሔዋንም ፡ ለፍጹም ፡
ጥፋት ፡ ይሆናሉ ፡ አንድም ፡
ኢኮነ ፡ ደብር ፡ ገብረ ፡ ዓበይት ፡
ነቢያት ፡ አሪትን ፡ ነዋሪት ፡
ቀዋሚት፡ ሕግ ፡ ናት ፡ ብለው ፡
እንዳላስተማሩ ፡
ወኢወግር ፡ ለብእሲት ፡ አመተ ፡
ደቂቅ ፡ ነቢያትም ፡ አምሳል ፡
መርገፍ ፡ የምትሆን ፡ አሪትን ፡
ነዋሪት ፡ ሕግ ፡ ናት ፡ ብለው ፡
እንዳላስተማሩ ፡ ምዬ ፡ እነግራ
ችኋለሁ ፡ ከመዝ ፡ ኃጢአት ፡
ኢተፈነወት ፡ አሁን ፡ እንደተ
ናገርሁት ፡ ኃጢአትም ፡ ነዋሪት
ሕግ ፡ ሁና ፡ አልተሠራችም ፡
አላ ፡ ሰብእ ፡ እምርእሰሙ ፡
ፈጠርዋ ፡ ቢጽ ፡ ሐሳውያን ፡
ልብ ወለድ ፡ አንቅተው ፡
ቀዋሚት ፡ ሕግ ፡ ናት ፡ ብለው ፡
አስተማሯት ፡ እንጂ ፡
ወለመርገም ፡ ዓቢይ ፡ ይከውኑ ፡
ቢጽ ፡ ሐሳውያን ፡ ለጽኑ ፡ መር
ገም ፡ ይሆናሉ፡ (ሑሩ ፡ እምኔየ ፡
ይባላሉ ፡)

፲፰ ፡ ወምክንት ፡ ለብእሲት ፡ ኢተ
ውህበ ፡
ለሴት፡ ምክንት፡ አልተሰጣትም፡
አላ ፡ በግብረ ፡ እደዊሃ ፡ ትመውት ፡
ዘእንበለ ፡ ውሉድ ፡

በእጇ ፡ ይዛ ፤ በቃሏ ፡ ተናግራ ፤ በሠራችው ፡ ኃጢአት ፡ ያለልጅ ትሞታለች ፡ እንጂ ፤ ኢሳይያስ ፡ አነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘእፈጥር ፡ መካነ ፡ ወአወልድ ፡ አለ ፤ ከዚህ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፤ አይጣላም? ቢሉ ፡ አይጣላም ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ሄኖክ ፡ ነው ፤ ምክንት ፡ በደዌ ፡ በኃጢአት ፡ ነው ፤ አነ ፡ ዘእፈጥር ፡ መካነ ፡ አለሳ ፡ ቢሉ ፡ እስከት ወልድ ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፤ አነ ፡ ዘእፈጥር ፡ መካነ ፡ አለ ፤ አንድም ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ የወለዱት ፡ ልጅ ፡ ይጠቅማልና ፡ እስኪወልዱ ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ ዘእፈጥር ፡ መካነ ፡ አለ ፤ አንድም ፡ መጻእ ያትን ፡ አለማወቅ ፡ ለነፍስ ፡ አልተሰጣትም ፤ አላ ፡ በእንተ ፡ ግብረ ፡ እደዊሃ ፤ በኃጢአቷ ፡ ምክንያት ፡ መጻእያትን ፡ ሳትና ገር ፡ ትሞታለች ፡ እንጂ ፤

፭ ፤ መሐልኩ ፡ ለክሙ ፡ ኃጥአን ፡ በቅዱስ ፡ ወዓቢይ ፤ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ግብርክሙ ፡ እኩይ ፡ ክሡት ፡ ውእቱ ፡ በሰማያት ፤

ኃጥአን ፡ ክፉ ፡ ሥራችሁ ፡ ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ የተገለጸ ፡ እንደሆነ ፤ ወአልብክሙ ፡ ግብረ ፡ ግፍዕ ፡ ክዱን ፡ ወኢኅቡዕ ፤

የተሠወረ ፡ የግፍ ፡ ሥራም ፡ እንደሌላችሁ ፡ በገናና ፡ በክበረ ስሙ ፡ ምዬ ፡ ነገርኋችሁ ፤

፷፩ ፤ ወኢታምስሉ ፡ በመንፈስክሙ ፤ በልቡናችሁ ፡ የሚሰወር አታስ መስሉት ፤

ወኢትበሉ ፡ በልብክሙ ፡ በልቡናችሁ ፡ ይሰወርልናል ፡ አትበሉ ፤

እስመ ፡ ኢተአምሩ ፡ ወኢትሬእዩ ፡ ኵሉ ፡ ኃጢአተክሙ ፡ ዘበሰማይ ፡ ይጸሐፍ ፡ ሁሉ ፡ በኵሉ ፡ ዕለት ፡ በቅድሜሁ ፡ ለልዑል ፤

በሰማይ ፡ በጌታ ፡ ፊት ፡ ይጻፍ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ አታዩም ፤ አታውቁምና ፤

፷፪ ፤ ወእምይእዜ ፡ ተአምሩ ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ግፍዕክሙ ፡ ዘተ ገፍዑ ፡ ይጸሐፍ ፡ በኵሉ ፡ ዕለት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ኵነኔክሙ ፤

ፍርድ ፡ እስከሚፈረድባት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ የበደላችሁት ፡ በደል ፡ በየቀኑ ሁሉ ፡ እንዲጻፍባችሁ ፡ ታውቃ ላችሁ ፤

፷፫ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ አብዳን ፡ እስመ ፡ ትትኃጐሉ ፡ በዕበድክሙ ፤

ብስንፍናችሁ ፡ ትጠፋላችሁና ፡
እናንተ ፡ ሰነፎች ፡ ወዮላችሁ ።
ወለጠቢባን ፡ ኢትሰምዕዎሙ ፡
መምህራንን ፡ አትሰሟቸውም ፤
ወሠናይ ፡ ኢይረክበክሙ ።
መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ አይሰጣ
ችሁም ፤

፴፬ ፤ ወይእዜኒ ፡ አእምሩ ፡ ከመ ፡
ድልዋን ፡ አንትሙ ፡ ለዕለተ ፡
ኀጉል ፤
አሁንም ፡ ጥፋት ፡ ለታዘዘባት ፡
ቀን ፡ እናንተ ፡ የተዘጋጃችሁ ፡
እንደሆናችሁ ፡ ዕወቁ ፤
ወኢትሰፈዉ ፡ ከመ ፡ ትሕየዉ ፡ ኃጥ
አን ፡ አላ ፡ ተሐውሩ ፡ ወትመውቱ ፤
ተፈርዶባችሁ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ትሄዳላችሁ ፡ እንጂ ። እንድናለን ።
ብላችሁ ፡ ተስፋ ፡ አታድርጉ ፤

፴፭ ፤ ወትመውቱ ፡ እስመ ፡ ኢት
አምሩ ፡ ቤዛ ፤
ምግባር ፤ ሃይማኖት ፡ የላች
ሁምና ፤
እስመ ፡ ተደለውክሙ ፡ ለዕለተ ፡
ኵነኔ ፡ ዓባይ ።
ለዕለተ ፡ ምጽአት ፡ (ጥፋት ፡ ለታ
ዘዘባት ፡ ቀን ፡) ስለ ፡ ተዘጋ
ጃችሁ ፤
ወለዕለተ ፡ ምንዳቤ ፡ ወኀሣር ፡ ዓቢይ
በመንፈስክሙ ፤

በመከራ ፡ ቀን ፡ በነፍሳችሁ ፡
ታላቅ ፡ ጕስቍልና ። ትቀበላላ
ችሁና ፤ ትሞታላችሁ ፤

፴፮ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ ግዙፋነ ፡ ልብ ፡
እለ ፡ ትገብሩ ፡ እኩየ ።
ክፉ ፡ ሥራን ። የምትሠሩ ፡ ልበ
ደንጋዮች ፡ ወዮላችሁ ።
ወትበልዑ ፡ ደመ ፤
ደምን ፡ የምትበሉ ፤ ደሙን ፡
አርግተው ፤ ቀቅለው ፡ ይበሉ
ታልና ፤ አንድም ፡ ብርንዶውን ።
ይበሉታልና ፤
እምአይቴ ። አንትሙ ፡ ትበልዑ ፡
በሠናይ ፡ ወትሰትዩ ፡ ወትጸግቡ ።
በጎ ፡ አድርጋችሁ ፡ ከወዴት ፡
አግኝታችሁ ፡ ትበላላችሁ ? ትጠ
ጣላችሁ ? ትጠግባላችሁ ?
እስመ ፡ እምኵሉ ፡ ሠናይ ፡ ዘአፈ
ድፈደ ፡ እግዚእነ ፡ ልዑል ፡ ዲበ ፡
ምድር ፤
በዓለም ፡ ላይ ፡ ልዑል እግዚአ
ብሔር አብዝቶ የፈጠረው ።
ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ መልካም ፡
ነው ፡ እያላችሁ ፡ በትድላ ፡
በደስታ ፡ ትበላላችሁ ፡ ትጠጣ
ላችሁ ፤ ወርእየ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከመሠናይ ፡ ካለው ። ሳትለዩ ፤
ሁሉን ፡ ትበላላችሁና ፤ አንድም ፡

ብሉ ፤ ካለው ፤ ወጥታችሁ ፡ አትብሉ ፡ ያለውን ፡ ትበላላችሁና ፤

ወአልብክሙ ፡ ሰላም ፤
አንድነትም ፡ የላችሁምና ፤

[redacted] ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ታፈቅርዋ ፡ ለግብረ ፡ ዓመፃ ፤
የበድልን ፡ ሥራ ፡ ለምትወዷት ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችሁ ፤
ለምንት ፡ ለክሙ ፡ ትሴፈውዋ ፡ ለሠናይት ፤
በጉዱቱንስ ፡ ሥራ ፡ ለምን ፡ ትመኟታላችሁ ፤

፲፪ ፤ አእምሩ ፡ ከመ ፡ ሀለወክሙ ፡ ትትወሀቡ ፡ በእደዊሆሙ ፡ ለጻድቃን ፤
በጻድቃንም ፡ እጆች ፡ አልፋችሁ ትያዙ ፡ ዘንድ ፡ እንዳላችሁ ፡ ዕወቁ ፤
ወይመትሩ ፡ ክሳውዲክሙ ፡ ወይቀትሉክሙ ፡ ወኢይምሕሩክሙ ፤
ቾብቾቢችሁን ፡ ይቈርጢችኋል ፡ የሚቈርጢቸው ፡ ሁነው ፡ አይደለም ፤ እነርሱን ፡ በበደሉበት ፡ በዚያ ፡ ፍዳ ፡ እንዲመጣባቸው ለማጠየቅ ፡ ነው ፤

፲፫ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትትፌሥሑ ፡ በምንዳቤሆሙ ፡ ለጻድቃን ፡ እስመ ፡ መቃብር ፡ ኢይትከረይ ፡ ለክሙ ፤
እናንተ ፡ መቃብር ፡ አይቈፈርላችሁምና ፤ በጻድቃን ፡ መከራ ፡ ደስ ፡ ለሚላችሁ ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችሁ ፤

[redacted] ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ታበጥሉ ፡ ነገረ ፡ ጻድቃን ፤
የጻድቃንን ፡ ነገር ፡ የምትንቁ ፡ የምታቃልሉ ፤ አንድም ፡ የመምህራንን ፡ ነገር ፡ የምታፈርሱ ፡ ወዮላችሁ ፤
እስመ ፡ ኢይከውን ፡ ለክሙ ፡ ተስፋ ፡ ሕይወት ፤
የድኅነት ፡ አለኝታ ፡ አይደረግላችሁምና ፤

፲፭ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትጽሕፉ ነገረ ፡ ሐሰት ፡ ወነገረ ፡ ረሲዓን ፤
የሐሰተኞችን ፡ መምህራን ፡ ነገር ፡ የምትጽፉ ፡ ወዮላችሁ ፡
እስመ ፡ ውእቶሙ ፡ ይጽሕፉ ፡ ሐሰቶሙ ፡ ከመ ፡ ይስምዕዋ ፡ ወኢይርስዕዋ ፡ ለዕበድ ፤
መምህራኖች ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ይሰሙት ፤ ዘንድ ፡ ሐሰታቸውን ፡ ይጽፋሉና ፤

፲፮ ፤ ወኢይከውን ፡ ሎሙ ፡ ሰላም ፡ አላ ፡ ሞተ ፡ ይመውቱ ፡ ፍጡነ ፡ ወኢይትነድዩ ፤

ፍቅር ፡ አንድነት ፡ አይደረግ ላቸውም ፤ ፈጥነው ፡ ይሞታሉ እንጂ ፤ አይዘገዩም ።

ጉባዔ

፴፫ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ ለእለ ፡ ይገብሩ ፡ ርስዕናተ ፤

ክፉ ፡ እርጅናን ፡ ለምታረጁ ፤ አንድም ፡ ክፉ ፡ ዝንጋዔን ፡ ለም ትዘነጉ ፡ ሰዎች ፤ ወዮላችሁ ፤ በጎ ፡ እርግና ፡ ክፉ ፡ እርግና ፤ አለ ፤ በጎ ፡ እርግና ፡ ለሰው ፡ ጽድቅም ፡ ኃጢአትም ፡ ይስማ ማዋል ፤ ሲያረጅ ፡ የቀደመው ፡ ኃጢአቱን፡ አስቦ ፡ ንስሐ ፡ገብቶ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታርቆ ፡ አቀ ጣሮ ፡ አድርሶ ፤ ይሞታል ፤ ክፉ ፡ እርግና ፡ አመንዝራ ፡ ሽማግሌ ፡ አቃጣሪ ፤ ይሆናል ፡ እንዲሉ ፤ እኛ ፤ በሕፃንነታችን ጊዜ ፡ ነፍስ ፡ እንገድል ፡ እን ሰርቅ ፡ እንቀማ ፤ ነበር ፤ የዛሬ ዘመን ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ ኃይል ፡ አለው ፡ እያለ ፡ ሰውን ፡ ያነሳሣል ፤ ወነገረ ፤ ሐሰት ፡ ይሴብሑ ፡ ወያ ክብሩ ፤

የሐሰት ፡ ነገርን ፡ ለሚያከብሩ ፤ ለሚያመሰግኑ ፤ ሰዎች ፤ ወዮላ ቸው ፤

ተጎጉልክሙ ፡ ወአልብክሙ ፡ ሕይ ወት ፡ ወሠናያት ፤

በዚህም ፡ ሥራችሁ ፡ጠፋችሁ ፡ ድኅነት ፡ ሰላማዊ ፡ ነገር ፡ የላችሁም ፤

፴፬ ፤ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትዌልጥዎሙ ፡ ለነገራተ ፡ ርትዕ ፡ ወሥር ዓተ ፡ እንተ ፡ ለዓለም ፡ የዐልዉ ፤

የቀኑ ፤ ነገሮችንም ፡ ለምትለ ዋውጧቸው ፤ ለእናንተ ፤ ወዮላ ችሁ ፤ ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖረውንም ፡ ሥርዓት ፡ ይለውጣሉ ፤

ወይሬስዩ ፡ ርእሶሙ ፡ ዘኢኮኑ ፤ ኃጥ አነ ፤ ዲበ ፤ ምድር ፡ ሀሰዉ ፡ ይትከ የዱ ፤

ራሳቸውንም ፡ ኃጢአተኛ ፡ ያላ ደረጉ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፤ ዓለም ፤ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፲፫

፩ ፤ በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ተደለዉ ፤ ጻድቃን ፡ ከመ ፡ ትንሥኡ ፡ ጸሎታ ቲክሙ ፡ ለተዝካር ፤

በእነዚያም ፤ ወራቶች ፡ ጻድቃን፡ ለበጎነታችሁ ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን፡ የለመናችሁትን ፡ ዋጋ ፡ ትቀበሉ ፤ ዘንድ ፡ ተዘጋጁ ፤

፪ ። ወእንበርከምዎሙ ፡ ለማዕተ ፡
በቅድመ ፡ መላእክት ፡ ከመ ፡ ያነብ
ርዎ ፡ ለኃጢአት ፡ ኃጥአን ፡ ቅድመ
ልዑል ፡ ለተዝካር ፤

ለክፉ ፡ መታሰቢያ ፡ ሲሆን ፡
ኃጥአን፡ ኃጢአታቸውን ፡ በጌታ
ፊት ፡ እንዲያኖሩ ፤ ጻድቃን ፡
ለበጎ ፡ መታሰቢያ ፡ ሲሆን ፡ ምግ
ባር ፣ ሃይማኖታቺሁን ፡ በ፯ቱ ፡
መላእክት ፡ ፊት ፡ አኖሯችኋ
ችው ፤

፫ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ይት
ሀወኩ ፡ አሕዛብ ፤

በእነዚህም ፡ ወራቶች ፡ አሕዛብ፡
ይታወካሉ ፤

ወይትነሥኡ ፡ አዝማደ ፡ አሕዛብ ፡
በዕለት ፡ እንተ ፡ ኀጕል ፤

ያልታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ አንድም
እለ ፡ ሰናክሬም ፤ አንድም ፡ የእለ፡
ሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ወገኖች ፡
ይነሣሉ ፤

፬ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ እለ
ይጼነሱ ፡ ይወፅኡ ፤

ከልብስ ፣ ከምግብ ፣ የተቸገሩ ፡
ሰዎች ፡ እለ ፡ ሰናክሬምን ፡ ተከ
ትለው ፡ ይወጣሉ ፤

ወይመስጡ ፡ ደቂቆሙ ፡ ወይገድፍ
ዎሙ ፡ ለደቂቆሙ ፤

አሕዛብ ፡ ልጆቻቸውን ፡ እየነ
ጠቁ ፡ ይጥሏቸዋል ፤ አንድም፡
እናት ፡ አባቶቻቸው ፡ መከራ ፡
ሲበዛባቸው ፡ ይጥሉአቸዋል ፤

፭ ፤ ወእምኔሆሙ ፡ ይድኅፁ ፡
ውሉዶሙ ፤

ከአሕዛብ ፤ አንድም ፡ ከእናት ፡
ከአባቶቻቸው ፡ የተነሣ ፡ ልጆቻ
ቸው ፡ ይሰነካከላሉ ፤

ወእንዘ ፡ ይጠብዉ፡ ይገድፍዎሙ ፡
ለደቂቆሙ ፤

አሕዛብ ፤ አንድም ፡ እናት ፡
አባቶቻቸው ፡ ሲጠቡ ፡ ልጆቻ
ቸውን ፡ እየወጉ ፡ ይጥሏቸዋል ፤

[illegible] ፤ ወኢይገብኡ ፡ ኀቤሆሙ ፤

እናት፡ አባቶቻቸው፡ ለማንሣት፤
አንድም ፡ አሕዛብ ፡ በርኅራኄ ፡
ወደ ፡ ውሉድ ፡ አይመለሱም ፤

ወኢይምሕርዎሙ ፡ ለፍቁራኒሆሙ ፤

አሕዛብ ፡ ለወዳጆቻቸው ፡ ለው
ሉድ ፣ ለግዳይ ፣ ለሰለባ ፡ አያ
ዝኑላቸውም ፤ አንድም ፡ እናት ፡
አባቶቻቸው ፡ ለሚወዷቸው ፡ ለል
ጆቻቸው ፡ አያዝኑላቸውም ፤ አይ
ራሩላቸውም ።

፯ ፤ ወካዕበ ፡ አነ ፡ እምሕል ፡ ለክሙ ፡
ለኃጥአን ፡ እስመ ፡ ለዕለተ ደም ፡
ዘኢየኀድዕ ፡ ተደለወት ፡ ኃጢአት ፤

የማይገታ ፡ የማይፈጸም ፡ ደም ለሚፈስስበት ፡ ቀን ፡ ኃጢአት ፡ ተዘጋጅቷልና ፡ ለእናንተ ፡ ለኃጥአን ፡ ጻግመኛ ፡ እምልሳችኋለሁ ፤ እነግራችኋለሁ ።

፯ ፤ ወይሰግዱ ፡ ለዕብን ፤
ወለእለ ፡ ይሰግዱ ፡ ሲል ፡ ነው ፣
ለደንጊያ ፡ ለሚሰግዱ ፡ ሰዎች ፤
ወእለ ፡ ይገልፉ ፤
ወለእለ ፡ ይገልፉ ፡ ሲል ፡ ነው ፣
ለጣዖት ፡ ለሚሰግዱ ፤ ጣዖት ፡ ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ።
ምስለ ፡ ዘወርቅ ፡ ወዘብሩር ፤
የወርቅ ፡ የብር ፡ ምስል ፡ ለሚሠሩ ፤
ወዘዕፅ ፡ ወዘልሕኵት ፤
ከእንጨትና ፡ ከሸክላ ፡ ተቀርጾ ለሚሠራ ፡ ምስል ፤

[illegible] ፤ ወእለ ፡ ይሰግዱ ፡ ለነፍሳት ፡ ርኩሳን ፤
ለረከሱ ፡ ለረቂቃን ፡ለግዙፋን ፤
ወለአኩያን ፡ አጋንንት ፤
ለክፉዎችም ፡ አጋንንት ፡ ለረቂቃን ፤ አንድም ፡ ለነፍሳት ፡ ለርኩሳን ፡ ሰዎች ፤ ወለአጋንንት ፤ በቁሙ ፡ ለአጋንንት ፡ ለሚሰግዱ ሰዎች ፤
ወለኵሉ ፡ ጣዖት ፡ ወለምሕራማት ፤
ለጣዖቱም ፡ ለመስገጃው ፡ ሁሉ ፡ ይሰግዳሉ ።

፲ ፤ ወኵሉ ፡ ረድኤት ፡ ኢይትረከብ ፡ እምኔሆሙ ፤
እምኔሆሙ ፡ ለጣዖታት ፡ ነው ፣
ከእነርሳቸውም ፡ ከጣዖታት ፡ ረድኤት ፡ ሁሉ ፡ አይገኝም ፤
ወይትረስዑ ፡ በእንተ ፡ ዕበደ ፡ ልቦሙ ፤
ከልቦናቸውም ፡ ድንቁርና ፡ የተነሣ ፡ ከሥላሴ ፡ ልቡና ፡ ይዘነጋሉ ፤
ወይጼልላ ፡ አዕይንቲሆሙ ፡ በፍርሀተ ልቦሙ ፤
በልቦናቸው ፡ ፍርሀት ፡ የልቡና ቸው ፡ ዓይኖች ፡ በድንቁርና ፡ ይያዛሉ ፤

፲፩ ፤ ወበርእየ ፡ አሕላሞሙ ፡ በሙ ይረስዑ ፤
የሐሰት ፡ ሕልም ፡ አለምን ፣ አለ ምን ፡ በማለታቸው ፡ ሕገ ፡ እግ ዚአብሔርን ፡ ይዘነጋሉ ፤
ወይፈርሁ ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ግብሮሙ ፡ በሐሰት ፡ ገብሩ ፤
ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ በሐሰት ፡ ሠርተዋልና ፡ ይፈራሉ ፤
ወሰገዱ ፡ ለዕብን ፡ ወይትገኑ ፡ በምዕር ፤
ለደንጊያውም ፡ ሰግደዋልና ፡ ፈጥነው ፡ ይጠፋሉ ፤

፲፪ ፡ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ብፁዓን ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትሜጠዉ ፡ ነገረ ፡ ጥበብ ፡ ወየአምርዋ ።

በእነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የጥበብን ነገር ፡ የሚቀበሉ ። የሚወዷት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ።

፲፫ ፡ ወይገብርዎን ፡ ለፍናዋተ ፡ ልዑል ፡ ወየሐውሩ ፡ በፍናወ ፡ ጽድቅ ።

ሕግን ፡ አውቀው ፡ ግብር ፡ ገብተው ፡ ሕግን ፡ የሚሠሩ ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ ናቸው ።

ወኢይረስዑ ፡ ምስለ ፡ እለ ፡ ይረስዑ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይድኅኑ ።

ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከሚዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ የማይዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ ይድናሉና ።

፲፬ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትሰፍሑዋ ፡ ለእኪት ፡ ለቢጽክሙ ።

በባልንጀሮቻችሁ ፡ ላይ ፡ ክፋትን አብዝታችሁ ፡ ለምትሠሩአት ፡ ወዮላችሁ ።

እስመ ፡ በሲኦል ፡ ትትቀተሉ ።

በሲኦል ፡ ትጠፋላችሁና ።

፲፭ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትገብርዋ ፡ ለመሠረተ ፡ ኃጢአት ፡ ወጕኅሉት ።

ክህደትን ። ፍቅረ ፡ ንዋይን ፡ ለምታደርጉ ፡ ወዮላችሁ ።

ወእለ ፡ ታመርሩ ፡ ዲበ ፡ ምድር ።

በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰውን ፡ የምታሳዝኑ ።

እስመ ፡ ቦቱ ፡ ትትዌድኡ ።

በእርሱ ፡ ትጠፋላችሁና ።

፲፮ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ተሐንፁ በፃማ ፡ ባዕድ ።

የሰው ፡ ከብት ፡ ቀምታችሁ ። ደመወዝ ፡ ነሥታችሁ ። ቤታችሁን ፡ ለምትሠሩ ፡ ወዮላችሁ ።

ወኵሉ ፡ መንድቆሙ ፡ ግንፋል ።

ሕንፃቸው ፡ ጡብ ፡ ስሆነ ።

ወዕብነ ፡ ኃጢአት ።

በኃጢአት ፡ ደንጊያ ፡ የድህ ፡ ደንጊያ ፡ ቀምተው ፡ ቤታቸውን ፡ ለሚሠሩ ፡ ወዮላቸው ።

እብለክሙ ፡ ከመ ፡ አልብክሙ ፡ ሰላም ።

እንድነት ፡ እንደሌላችሁ ፡ እኔ ፡ እነግራችኋለሁ ።

፲፯ ፡ አሌ ፡ ሎሙ ፡ ለእለ ፡ ይሜንኑ ፡ መስፈርተ ፡ ወርስተ ፡ [redacted] ሆሙ ፡ እንተ ፡ ለዓለም ።

የአባቶቻቸውን ፡ ሃይማኖት ። የአባቶቻቸውን ፡ ሥርዓት ፡ ለሚንቁ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ።

ወያተልዉ ፡ ነፍሰሙ ፡ ድኅረ ፡ ጣዖት ፡

የአባቶቻቸውን ፡ ሥርዓት ፤ የአባቶቻቸውን ፡ ሃይማኖት ፤ ትተው ፡ ልቡናቸውን ወደ ፡ ጣዖት ፡ ለሚመልሱ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ።

እስመ ፡ ኢይከውን ፡ ሎሙ ፡ ዕረፍት ።

ንው ፡ ኅቤየ ፡(ኑ ፡ ወደ ፡ እኔ) ፡ ተብለው ፡ ዕረፍተ ፡ ነፍስን ፡ አያገኙምና ።

፲፰ ፡ አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትገብርዋ ፡ ለዓመፃ ፡ ወትረድእዋ ፡ ለግፍዕ ፡

በደልን ፡ የምትሠሯት ፤ ግፍንም ፡ ለምትፈጽሟት ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችሁ ።

ወትቀትሉ ፡ ቢጸክሙ ፡ እስከ ፡ ዕለተ ኵነኔ ፡ ዓባይ ።

ፍርድ ፡ እስከሚፈጸምባት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ፡ ባልንጀሮቻችሁን ፡ ለምትገድሉ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ።

እስመ ፡ ያወድቅ ፡ ስብሐቲክሙ ።

ጌትነታችሁን ፡ ያጠፋልና ።

ወይወዲ ፡ እከየ ፡ ውስተ ፡ ልብክሙ ።

በልቦናችሁ ፡ ብስጭትን ፡ ያሳድራልና ።

፲፱ ፡ ወያነሥእ ፡ መንፈሰ ፡ መዓቱ ፡ ያኀጕልክሙ ፡ ለኵልክሙ ።

በሰይፍ ፡ ያጠፋችሁ ፡ ዘንድ ፡ ቁጣውን ፡ የሚፈጽምበት ፡ ሥልጣኑን ፡ ያነሳል ።

ወኵሎሙ ፡ ጻድቃን ፡ ወቅዱሳን ፡ ይዜከሩ ፡ ኀጢአተ ፡ ዚአክሙ ።

ደናግልና ፡ ሕጋውያንም ፡ ሁሉ ኀጢአታችሁን ፡ ያስባሉ ።

፳ ፡ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ በ፩ዱ ፡ መካን ፡ አበው ፡ ምስለ ፡ ውሉዶሙ ፡ ይትጓድኡ ።

በእነዚያም ፡ ወራት ፡ አባቶች ፡ ከልጆቻቸው ፡ ጋራ ፡ በአንድ ፡ ቦታ ፡ ተቀራድደው ፡ ያልቃሉ ።

ያልታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ ካልታወቀ ፡ ቦታ ፡ እሰስናክሬም ፡ በለኪሰን ፡ እለ ፡ ሐሳዊ ፡ መሲሕ ፡ በመጌዶን ።

፳፩ ፡ ወአኃው ፡ ምስለ ፡ ቢጾሙ ፡ ይወድቁ ፡ በሞት ፡ እስከ ፡ ይውኅዝ ፡ ከመ ፡ ተክዚ ፡ እምደመ ፡ ዚአሆሙ ፡

ከእነርሱ ፡ ደም ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውሀ ፡ እስኪፈስስ ፡ ድረስ ፡ አንድም ፡ ደማቸው ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡ በዝቶ ፡ እስኪፈስስ ፡ ድረስ ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ጋራ ፡ በሞት ፡ ይጠፋሉ ።

